# Table of Contents

ምዕራፍ አንድ

1. በነጭ ወረቀት አዲስ ሰውን የማምጣት ዘዴ

★ በነጭ ወረቀት አዲስ ሰውን የማምጣት ዘዴ(በነጭ ወረቀት የወንጌል ስብከት ዘዴ)

1. አዲስ ሰውን መቅረብ

2. ወንጌልን መስበክ

● ዮሐ. 5÷24:- እውነት እውነት እላችኃለሁ ቃሌን የሚሰማ የላከኝንም የሚያምን የዘላለም ህይወት አለው፤ ከሞትም ወደ ህይወት ተሻገረ እንጂ ወደ ፍርድ አይመጣም፡፡

በእውነት አንተ (አንቺ፣ እናንተ፣ እርስዎ) ከዚህ ታሪክ እንደንምረዳው የተኛውን በኩል ኑሮ ይፈልጋሉ ትፈልጋለህ(ትፈልጋለሽ)?

መልስ፡- በቀኝ በኩል ያለው ኑሮ የሚፈልጉ ከሆነ ኢየሱስ ክርስቶስን እንደ ግል አዳኝና ጌታ አድርገው መቀበል ያስፈልጋል በዚህ የተስማሙ የተስማማ ከሆንህ(ሽ) እኔ ስለ አንተ/አንቺ ስለ እረሶዎ ጌታን ልፀልይ፡፡ ከእኔ በኃላ ይህን ፀሎት ፀልይ

3. ጌታ ኢየሱስ ክርስቶስን የሚቀበል ሰው ፀሎት፡-

ውድ እግዚአብሔር ሆይ፡ እኔ ኃጢአተኛ ነኝ፤ ኢየሱስ ክርስቶስን አሁን ወደ ልቤ እንድገባ ፈቅጀአለሁ፤ የእኔን ኃጢአት ሁሉ በመስቀል ላይ ባፈሰስከው በደምህ በኩል እጠብልኝ ኃጢያትንም ይቅር በል፤ የዘላለምን ህይወት ስጠኝ፤ አሁን ኢየሱስ ክርስቶስ፡ አንተን የሕይወቴ ጌታና አዳኝ አድርገ ተቀብየዋለሁ፤ እግዚአብሔር አባቴ ሁንልኝ እኔ ያንተ ልጅ እሆናለሁ፤አሁን እኔን ስላዳንክ፡ ከኃጢአቴም ስላነፃኸኝ ስሜንም በሕይት መጻሐፍ ስለጻፍክልኝ አመሰግናለሁ፡፡ ከአሁን ጀምሮ ካንተ ጋር ለዘላለም አኑረኝ በኢየሱስ ክርስቶስ ስም አሜን፡፡

4. አሁን አንተ ማመንህን የሚያረጋግጡ 6 ጥያቄዎች

① ኢየሱስ አሁን የት አለ?

መልስ ፡- በልቤ ውስጥ

② የአንተ ኃጢአት ሁሉ ምን ሆነ?

መልስ፡ - ኃጢአቶቼ ሁሉ ተደምስሰዋል፤ በኢየሱስ ክርስቶስ ስም ይቅር ተብያለሁ።

③ ወደፊት ኃጢያት በሰራህ ጊዜ ምን ትሆናለህ?

መልስ፡ - ኃጢያትን ደግሜ ላለመስራት ንስሐ እገባለሁ

④ ኢየሱስ ላንተ ምንድን ነው?

መልስ፡ - የሕይወቴ አዳኝና ጌታ ነው፡ ፡

⑤ አንተ ደህንነትን መቼ ተቀበለህ?

መልስ፡ - አሁን ኢየሱስ ክርስቶስን ለመቀበል በፀልየሁት ጊዜ

⑥ አሁን አንተ ብትሞት ወደ መንግስተ ሰማይ የመግባት እምነት አለህ?

መልስ፡ - አዎን

ለምን?

መልስ፡ - ኢየሱስ ክርስቶስን እንደ ግል አዳኝና ጌታ አድርጌ ስላመንሁ፡ ፡

5. ጽኑ (ጠንካራ) ክርስቲያን መሆን - የሳንቲም ምሳሌ

♦ የመጽሐፍ ቅዱስ ቃል መግለጫ(ዮሐ. 10÷28-29)

እኔም የዘላለም ሕይወት እሰጣችኃለሁ ለዘላለምም አይጠፉም፤ከእጄም ማንም አይነጥቃቸውም፡ ፡ የሰጠኝ አባቴ ከሁሉ ይበልጣል፤ ከአባቴም እጅ ሊነጥቃቸው ማንም አይችልም፡ ፡

6. አዲስ ሰው ኢየሱስ ክርስቶስን ስያምን የእርሱን ሙሉ አድራሻ መፃፍ

- ስም

- ስልክ ቁጥር

- የመኖርያ አድራሻ

7. ያለ ማቈረጥ ለ24 ሰዓታት አዲስ ጌታን የተቀበለውን ሰው ማነጋገር

- በስልክ

- በአካል (ቀርቦ በማግኘት)

8. ማዘጋጀት

ነጭ ወረቀት፣ እስክርብቶና እርሳስ አዘጋጅቶ ያመኑ ሰዎችን መመዝገብ

አዲስ ሰውን በህብረት ፈልጎ የማግኘት መንገድ ፡-ሰዎችን ወደ ቤተክርስቲያን ለማምጣት አንደኛ ምክንያት ከሰዎች ተገናኝቶ መጠያየቅ ነው፡፡ ኢየሱስ ክርስቶስ ያመኑ ሰዎችን እንዴት እንዳመኑ ስንጠይቃቸው ከ75-90% ከሰዎች ጋር ማለትም ከዘመዶቻቸው ጋር ህብረት በማድረግ እንደሆነ ይገልፃሉ፡፡

በእኛ አካባቢ ያሉትን፤ ጌታን ያላመኑ ሰዎችን፤ ወደ ህብረታችን በማምጣት ጌታ ኢየሱስ ክርስቶስን እንደግል አዳኛቸው አድርገው እንዲቀበሉ መርዳት ያስፈልጋል፡፡ እኛ በብዙ ስለእነርሱ በማሰብ ወደ ጌታ ቤት ማምጣት ያስፈልጋል፡፡

★ በትንሽ ቡድን 12 ሳምንት ክፍት ስብሰባ የመስበክ ዘዴ.

ምዕራፍ ሁለት

2. በእምነት በነፃነት መኖር(ሉቃ.4÷18-19)

● ሉቃ.4÷18-19

18. “የጌታ መንፈስ በእኔ ላይ ነው፣ ለድኾች ወንጌልን እንድሰብክ፣ እግዚአብሔር እኔን ቀብቶኛልና፤ ለታሰሩት መፈታትን፣ ለዕውሮች ማየትን እንዳውጅና የተጨቈኑትንም ነጻ እንዳወጣ ልኮኛል፣

19. እንዲሁም ጌታ ሕዝቡን የሚያድንበትን የጸጋ ዓመት እንዳስታውቅ ልኮኛል፡፡”

ነፃ መውጣት ማለት ለእኛ የተለመደ ቃል ነው፡፡ እኛ ከኮምንስት አገዛዝ ማለትም አስራ ሰባት አመት ሙሉ ስገዛን ከነበረው አገዛዝ ነፃ መውጣት ማለት ነው፡፡ ይህን ነፃነት የመቀበል ልምድ አለን፡፡ ኢየሱስ ክርስቶስ ለሕይወታችን ለእምነታችንና ነፃነትን ለመስጠት መጣ፡፡ ኢየሱስ ደሃዎችን፣ ኃጢአተኞችን በርግማንና በፍርሃት ውስጥ ያለን ህመምተኞችን ከሞት ነፃ አውጥቶ በነፃነት ለማኖር ከሰማይ መጣ፡፡ የእግዚአብሔር ልጅ ኢየሱስ ክርስቶስ የሚሰጠው የእምነት ነፃነት ምንድን ነው? እኛስ እንዴት በዚህ ነፃነት እንኖራለን?

★ የክፍት ስብሰባ ሥራ

① ሕይወታችንን የምናገር ቃል መስበክ

ኢየሱስን ያላምነ አዲስ ሰው ህይወትን ስላላገኘ ህይወቱን የሚነካ (የሚለውጥ) ቃል መስበክ ያስፈልጋል፡፡

② ስለ ወንጌል የምናገር ቃል መስበክ፡፡ ወንጌል ማለት ኢየሱስ ክርስቶስ ነው፤ ኢየሱስ ክርስቶስ ለሕይወታችን መፍትሄ የሚሰጥ ነው፡፡

③ ኢየሱስ ክርስቶስ በአለም ላይ ንጉስ፣ ነብይ፣ ካህን እንደ ሆነ የምናገር ቃል መስበክ ያስፈልጋል፡፡

④ ስለ ተልዕኮ የምናገር ቃል መስበክ፡፡ ኢየሱስን ያላምነ አዲስ ሰው ተልዕኮ ስለሌው ስለተልዕኮ ምንነት የሚገልፅ ቃል መስበክ ያስፈልጋል፡፡

★ በሕይወት ስንኖር ማስታወስ ያለብን ነገሮች

① ከእግዚአብሔር ጋር በትክክል መኖራችንን ማስታወስ

② እግዚአብሔር አሁን እየሰራ መሆኑን ማስታወስ

③ እግዚአብሔር እምነት ላለው ሰው የተትረፈረፈ በረከት እንደሚሰጥ ማስታወስ፡፡

● ዕብ.11÷6

6-ያለእምነት እግዚአብሔርን ደስ ማሰኘት አይቻልም፤ ወደ እግዚአብሔር የሚቀርብ ሰው እግዚአብሔር መኖሩንና እርሱን ለሚፈልጉት ሰዎችም ስጦታን የሚሰጥ መሆኑን ማመን አለበት፡፡

④ እግዚአብሔርን ለሚያገለግል ሰው እግዚአብሔር የወደፊት በረከት እንደሚሰጥ ማስታወስ፡፡ ወንጌልን የሚሰብክ ሰው በሰማይ እንደፀዳል (እንደከዋክብት) ይደምቃል ይላል፡፡

● ዳን.12÷3

3-ጥበበኞቹም እንደ ሰማይ ፀዳል፥ ብዙ ሰዎችንም ወደ ጽድቅ የሚመልሱ እንደ ከዋክብት ለዘላለም ይደምቃሉ።

⑤ በዓለም ላይ ከኢየሱስ የሚበልጠውን ሥራ ልንሠራ እንደምንችል ማስታወስ

● ዮሐ.12÷14

14. ኢየሱስ የአህያ ውርንጭላ አገኘና በእርሱ ላይ ተቀመጠ፣ እንዲህ ተብሎ እንደ ተጻፈ፣

እግዚአብሔር የጽድቅን አክሊል ለመስጠት ተዘጋጅቷል፡፡

● 2ጢሞ.4÷8

8-ከእንግዲህ ወዲህ የጽድቅ አክሊል ተዘጋጅቶ ይጠብቀኛል፤ ይህንንም አክሊል ያ ትክክለኛ ፍርድን የሚሰኘ ጌታ ለእኔ ብቻ ሳይሆን የእርሱን መገለጥ ለሚወድዱ ሁሉ ነው፡፡

ውጤት፡- በኢየሱስ ክርስቶስ ስም ያመኑ የተትረፈረፈ በረከትን ይለማመዳሉ፤እኛ ክርስቲያኖች ለሌሎች ሰዎች ማለትም ስለ ስቃያቸውና ስለ ችግሮቻቸው መፍትሄ የሚሰጥ ስብከት ልንሰብክ ይገባል።

1. ድኾችን ነፃ ማውጣት

● ዘፍ.3÷16-19

16-ሴቲቱንም፣ “በእርግዝናሽ ወራት ጭንቀትሽን፣ በምትወልጂበትም ጊዜ የምጥ ሥቃይሽን አበዛሁ፤ ይህም ሁሉ ሆኖ ፍላጎትሽ ለባልሽ ይሆናል፡፡ ለእርሱም ታዛዥ ትሆኚአለሽ” አላት፡፡

17-አዳምንም እንዲህ አለው፣ “የሚስትህን ቃል ሰምተህ ‘አትብላ’ ያልኩህን ፍሬ ከዛፉ ወስደህ ስለ በላህ፣ አንተ በፈጸምከው ክፉ ሥራ ምክንያት ምድር የተረገመች ትሁን፤ በሕይወት ዘመንህ ሁሉ ምግብህን ከእርስዋ የምትበላው በብርቱ ድካም ነው፡፡

18-ምድር እሾኽና አሜከላ ታበቅላለች፤ አንተም የዱር ተክሎችን ትበላለህ፡፡

19-ወደ መጣህበት ወደ መሬት እስክትመለስ ድረስ፣ እንጀራህን በግንባርህ ላብ ትበላለህ፡፡” ዐፈር ነህና፣ ወደ ዐፈርም ትመለሳለህ፡፡

1) በሕይወታቸው ኃጢአት ከሠሩ በኋላ እግዚአብሔርን ትተው በመንፈሳቸውና በሥጋቸው ላይ ድህነት አመጡ፡፡

2) በመንፈስ ድኻ የሆኑ ሰዎች ፀባይ:-

① የዘላለም ሕይወት የላቸውም፡፡ እነዚህ ሰዎች የመንፈስ ድኾ ናቸው፡፡

② የእግዚአብሔር ቃል የላቸውም፡፡

③ ወደ መንግሥተ ሰማይ አይሄዱም፡፡

3) በሥጋ ድኻ የሆኑ ሰዎች ፀባይ

① የንብረት (ዕቃዎች) ማጣት ችግሮች ይከሰታል

② የገንዘብ እጦት ይከሰታል፡፡

③ የአካባቢ መራቆት

4) ኢየሱስ ክርስቶስ የእኛ ድህነታችን ሁሉ በራሱ ላይ ወስዶ የአብርሃምን በረከት ለእኛ ሰጠ፡፡

● ገላ.3÷13-14

13-"በእንጨት ላይ ተሰቅሎ የሚሞት ሁሉ የተረገመ ነው" ተብሎ ስለ ተጻፈ ክርስቶስ ስለ እኛ እንደ ተረገመ ሰው ሆኖ ሕግ ከሚያስከትለው ርግማን ዋጀን፡፡

14-ይህም የሆነው እግዚአብሔር ለአብርሃም የሰጠው በረከት በኢየሱስ ክርስቶስ አማካይነት ለአሕዛብ እንዲደርስና እኛም እግዚአብሔር እሰጣችኋለሁ ያለውን መንፈስ ቅዱስን በእምነት እንድንቀበል ነው፡፡

2. ከእስራት (በሰይጣን እስራት ውስጥ ያሉትን) ነፃ መውጣት

● 1ዮሐ.3÷8

8-ዲያብሎስ ከመጀመሪያው አንሥቶ ኃጢአት ስለሚሠራ ኃጢአትን የሚሠራ ሁሉ የዲያብሎስ ወገን ነው፡፡ የእግዚአብሔር ልጅ የተገለጠውም የዲያብሎስን ሥራ ለማፍረስ ነው፡፡

1) በኃጢአት እስራት ውስጥ ያሉት ሰዎችን ነፃ ማውጣት(የአዳም ኃጢአት፣ እንደገና የሠሩት ኃጢአትና የአያቶች ኃጢአት)

2) በጭንቀትና በፍርሃት ውስጥ ያሉትን ሰዎች ነፃ ማውጣት፤ በአካባቢ በጭንቀት ውስጥ፣ (ስለወደፊት ትዳር በማሰብ የሚጨነቁትን፣ ሞት ፍርሃት የሚጨነቁትን) ነፃ ማውጣት

3) በሰይጣን እስራት ውስጥ ያሉ ሰዎችን ነፃ ማውጣት

- መንፈሳዊ ህመም፣ መከራ፣ የአዕምሮ በሽተኛ (ዕብደት)

- የገብረ ገብነት ኃጢአት

4) በክፉ ፀባይ የተያዙ ሰዎችን ነፃ ማውጣት፤ በቁጣ፣ ጥላቻ፣ በጦርነት፣ በሐዘን ትዕግሥትን አላደርግም በማለት

በራሱ ኃጢአት የማድረግ ልምምድ ውስጥ ያሉትን ነጻ ማውጣት

5) በክፉ ልምድ ውስጥ የታሰሩ ሰዎችን ነፃ ማውጣት፤ ብዙ መጠጦችን በመጠጣ የሚሰክሩትን፣ ጫት የሚቅሙትን፣ በዝሙት፣ በስርቆት፣ በአደንዛዥ ዕጽ የታሰሩትን፣ በዕውቀት፣ በፍልስልና፣ በትምህርት ወዘተ... በእነዚህ ነገሮች ለተያዙ

ሰዎች ማንኛውም ሰው ስለችግሮቻቸው መፍትሄን አይሰጥም፡፡ ከእነዚህ ችግሮች ማን ነው ነፃ የሚያወጣው? መልሱ ኢየሱስ ክርስቶስ ነው፡፡

6) አሁን ኢየሱስ የታሰሩትን ወዲያውኑ ነፃ ያወጣል፡፡ ኢየሱስ ክርስቶስ አሁን በእኛ መካከል ይገኛል፡፡

● ዕብ.13÷8

8-ኢየሱስ ክርስቶስ ትናንትም ዛሬም ለዘለዓለምም ያው ነው፤ አይለወጥም፡፡

3. የማያዩትን ሰዎች ከጨለማ ነፃ ማውጣት

1) በተፈጥሮ ዓይን የታወሩ ሰዎችን ነፃ ማውጣት፤ የማያየው ሰው የበርጤሜዎስ ዓይን መከፈት

ኢየሱስ የበርጤሜዎስን ዓይን ከፈተ፡፡ ኢየሱስ የእኛንም ዓይን ሁሉ ይከፍታል፡፡

2) በእምነት የታወሩ ዓይኖች መክፈት፡- ሰው ብቻ ለዘላላም ለመውደድ ይፈልጋል፡

ስለዚህ በእኛ ውስጥ መንፈስ ቅዱስየመኖሩ ሁኔታን ያሳያል ማለት ነው፡፡

① በኤደን ገነት ውስጥ እግዚአብሔርን የሚያይ የመንፈስ ዓይን ተጋርዶ ነበር

② ከሞት በኋላ ምን እንዳለ አላውቁም

③ በምኞት የታወሩ ዓይኖች

3) ኢየሱስን በማመን አለምን የሚያይ ዓይን ይከፍታል፡፡ ኢየሱስ የሚሰጠውን የሕይወት ውሃ ለመጠጣትና ለነፍሱ ዕረፍትና ጥጋብን ለማግኘት ሰው ወደ እግዚአብሔር መሄድ ያስፈልጋል፡፡

● ዮሐ.4÷13-14

13. ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰላት፣ “ከዚህ ውሃ የሚጠጣ ሁሉ እንደገና ይጠማል፣

14. ነገር ግን እኔ ከምሰጠው ውሃ የሚጠጣ ለዘለዓለም ከቶ አይጠማም፣ እኔ የምሰጠው ውሃ በእርሱ ውስጥ ለዘለዓለም ሕይወት የሚፈልቅ የውሃ ምንጭ ይሆናል፡፡”

4. የአዕምሮ ህመምተኛ (የሚወተውተውን ሰው) ነፃ ማውጣት፡፡

● ሐዋ.10÷38

38-እግዚአብሔር የናዝሬቱን ኢየሱስ በመንፈስ ቅዱስና በኀይል ቀባው፤ ኢየሱስ መልካም ነገርን እያደረገ በዲያብሎስ የተያዙትን ሁሉ ፈወሰ፤ እግዚአብሔርም ከኢየሱስ ጋር ስለ ነበረ፡፡

1) በመንፈስ የተያዘ ሰው ነፃ መውጣት

2) የልብ ህመም 70% በላይ ከአእምሮ መወትወት ይመጣል

ሐዘንተኛ፣ ጭንቀት፣ ቁጣ ተስፋ መቁረጥ

3) በሥጋ ብዙ የሚታመሙትን ነፃ ማውጣት፤ ከጭንቀት፣ ከሀዘን፣ ከስቃይ የተነሳ ብዙ ችግሮች የሚወተውቱ ሰው ሰላም የላቸውም፡፡

4) በማህበራዊ ህግ ጭንቀት ውስጥ ያሉትን ነፃ ማውጣት ያስፈልጋል፡፡ አንድ ወንድ 4 ሴቶችን የማግባት መብት አለ ተብሎ የተወሰነው የሙስልም ሃይማኖት ህግ ሴቶችን በጭንቀት ውስጥ አስገብተአል፤ የሃይማኖት ልዩነት የተፈጥሮ ልዩነት ወዘተ…

5) አሁን ኢየሱስ በእነዚህ ጭንቀቶች ውስጥ የታሰሩትን ሰዎች ነፃ ለማውጣት ይፈልጋል፡፡

● ማቴ.11÷28

28. እናንተ ደከሞች ሸክማችሁ የከበደ ሁሉ ወደ እኔ ኑ፣ እኔም ለእናንተ ዕረፍት እሰጣችኋለሁ፡፡

5. አሁን የኢየሱስ ክርስቶስ የፀጋ ዓመት የምንሰብክበት ጊዜ ነው፡፡

● ሉቃ.4÷19

19. እንዲሁም ጌታ ሕዝቡን የሚያድንበትን የጸጋ ዓመት እንዳስታውቅ ልኮኛል፡፡”

1) ኢየሱስ ኢዮቤልን፤ መውጠትና ነፃነት በ3ኛው መስጠት መጣ፡፡

2) ኢየሱስ በመስቀል ላይ ሞቶ ተቀብሮ በ3ኛው ቀን ከተነሳ በኋላ የመንፈስ ቅዱስ ኃይል ስለሰጠን የፀጋ ዓመት የምንሰብክበት ጊዜ ነው፡፡

3) አሁን የእግዚአብሔር ማዳን፣በረከትና የምስራች ተናገር

4) ኢየሱስ ሕይወታችንን ያነፃናል፡፡

5) ኢየሱስ ጌታና አዳኝ አድርገን ስንቀበል ከሕይወታችን ችግሮችን ያስወግዳል፡፡

ምዕራፍ ሶስት

3. እውነተኛ ሰላምን የምናገኝበት መንገድ፡፡ (ፊልጵ.4÷4-7)

● ፊልጵ.4÷4-7

4-ሁልጊዜ በጌታ ደስ ይበላችሁ፤ ደግሜ እላለሁ፥ ደስ ይበላችሁ። 5-ገርነታችሁ ለሰው ሁሉ ይታወቅ።

6-ጌታ ቅርብ ነው። በነገር ሁሉ በጸሎትና በምልጃ ከምስጋና ጋር በእግዚአብሔር ዘንድ ልመናችሁን አስታውቁ እንጂ በአንዳች አትጨነቁ።

7-አእምሮንም ሁሉ የሚያልፍ የእግዚአብሔር ሰላም ልባችሁንና አሳባችሁን በክርስቶስ ኢየሱስ ይጠብቃል።

በዓለም የተሻለ ጥሩ ዋጋ ያለው ነገር ምንድን ነው? ያም የልብ ሰላም ነው፡፡ ሰላምን ተቀብለን በሰላም ሊንኖር ያስፈልጋል፡፡ በመልካም ስፍራ በመኖር የልብ ሰላም ከሌለ ምንድን ያደርጋል? አሁን ሰዎች ሁሉ በከባድ ሸክም ውስጥ ይኖራሉ፤ ይህ ሸክም ስለሞት ፍርሃት፣ ስለውድቀት ፍርሃት ወዘተ - - - ብዙዎች በኃጢአት ጭንቀት እየተሰቃዩ ይኖራሉ፡፡ ለእነዚህ ጭንቀቶች ሰዎች መፍትሄ ይሞከራል ብሎ ያስባሉ፤ ነገር ግን ያንን ሥልጣን አግኝቶ ከጭንቀታቸው አያርፉም፤ ታዲያ በሕይወታቸው በከባድ ሸክም ውስጥ ያሉትን ሰዎች የልብ ዕረፍትና ሰላምን የሚያገኙበት መንገድ ምንድን ነው?

★ ሰዎች ኢየሱስን የሚያገኙብት ሳይሆን ምክንኒያት ምንድን ነው?

① ስለ ኃጢአት ነው

● ኢሳይያስ.59÷1-2

1-እነሆ፥ የእግዚአብሔር እጅ ከማዳን አላጠረችም፥ ጆሮውም ከመስማት አልደነቈረችም

2-ነገር ግን በደላችሁ በእናንተና በአምላካችሁ መካከል ለይታለች፥ እንዳይሰማም ኃጢአታችሁ ፊቱን ከእናንተ ሰውሮታል።

② እውነት ሕይወት ስለሌለ፤ የእግዚአብሔር ልጅ እንደገና መወለደ አሳፈለገ፡፡

● ሮሜ.8÷16

16. የእግዚአብሔር መንፈስ ከእኛ መንፈስ ጋር ሆኖ የእግዚአብሔር ልጆች መሆናችንን ለእኛ ይመሰክራል፡፡

● ዮሐ.1÷12-13

12. ነገር ግን ኢየሱስ ራሱ ለተቀበሉትና በስሙ ላመኑት ሁሉ ሰዎች የእግዚአብሔር ልጆች የመሆን መብት ሰጣቸው፡፡

13. እነርሱም ከእግዚአብሔር ተወለዱ እንጂ ከደም ወይም ከሥጋ ፈቃድ ወይም ከሰው ፈቃድ አልተወለዱም።

③ ሰይጣን ስለሚቋቋም ነው::

● ማቴ.12÷28-29

28. ነገር ግን እኔ በእግዚአብሔር መንፈስ አጋንንትን የማስወጣ ከሆነ፥ እንግዲህ የእግዚአብሔር መንግሥት በእናንተ ላይ መጥታለች ማለት ነው፡፡

29. ደግመስ አንድ ሰው አስቀድመ ኀይለኛውን ሳያስር ወደ ኀይለኛው ቤት ገብቶ ንብረቱን መዝረፍ እንዴት ይችላል? ኀይለኛውን ካሰረው በኋላ ቤቱን መበዝበዝ ይችላል፡፡

④ የእውነት ግብና ዋጋ ስለጠፋ ነው::

● ሮሜ.3÷9-10

9. እንግዲህ ምን እንላለን? እኛ ከእነርሱ እንበልጣለንን? ከቶ አይደለም፤ አይሁድም ሆኑ አሕዛብ፥ ሁሉም ከኀጢአት በታች እንደሆኑ አስቀድመን ከሰናቸዋል፤

10. እንዲህ ተብሎ እንደ ተጻፈ፤ “ጻድቅ ማንም የለም፤ አንድም እንኳ፤

ሰዎች እውነተኛ ሰላምን ለማግኘት ብዙ ዓይነት ሙከራ ይሞክራሉ፡፡

1) 1,000 ሚስቶችን ያገባው ባለጠጋው ሶለሞን ሲናገር፤ ሁሉም ከንቱ ከንቱ የከንቱ ከንቱ ነው አለ፡፡ ይህ ማለት የልብ ሰላም ብዙ ሚስቶችን በማግባት አይገኝም ማለቱ ነው፡፡

● መክ.1÷1

1-በኢየሩሳሌም የነገሠ የሰባኪው የዳዊት ልጅ ቃል።

2) የእንግሊዝ ታዋቂውና ዝነኛ አክተር የቻፕሊንግ ከራሱ ሕይወት ሲናገር “የእኔ ሕይወት ብቸኛና ባዶ፣ ሰላም የሌለባት ሕይወት ናት” አለ፡፡ ታዋቂ ሰው መሆን የልብ ሰላም አያስገኝም፡፡

3) አክተር ማርሊን ሞሎ በ37 ዓመቱ የራሱን ህይወት አጠፋ፤ አክተር መሆን የልብ ሰላም አያስገኝም፡፡

4) የአሜሪካ ታላቅ ካምፓኒ ሴት ልጅን ያገባ ሰው ኤደል ዱፋንቲ ብቸኛ መሆኑን ካወቀ በኃላ ራሱን አጠፋ፤ የታዋቂ ካምፓኒያ ቤተዘመድ መሆን የልብ ሰላም አያመጣም፡፡

ዓለም የሚሰጠው ነገር ከንቱ ጭንቀትና ስቃይ ብቻ ነው፡፡

1) ሕይወት እንደ ማለዳ ጉም ናት፡፡

● ያዕ.4÷14

14-ነገ የሚሆነውን አታውቁም፤ ሕይወታችሁ ምንድን ነው? ለአንድ አፍታ ታይቶ በኋላ እንደ ሚጠፋ ጉም ናችሁ፡፡

2) ሕይወት እንደ ሜዳ አበባ ናት፡፡

● መዝ.103÷15

15-ሰውስ ዘመኑ እንደ ሣር ነው እንደ ዱር አበባ እንዲሁ ያብባል

3) ሕይወት በቀትን ጊዜ ድካምና ችግሮች መብዛት ነው፡፡

● ማቴ.11÷28

28. እናንተ ደከሞች ሸክማችሁ የከበደ ሁሉ ወደ እኔ ኑ፣ እኔም ለእናንተ ዕረፍት እሰጣችኋለሁ፡፡

4) ሕይወት በእውነተኛ ሲታይ ከንቱ ከንቱ የከንቱ ከንቱ ናት፡፡

● መክ.1÷2-3

2-ሰባኪው። ከንቱ፥ ከንቱ፥ የከንቱ ከንቱ ሁሉ ከንቱ ነው ይላል።

3-ከፀሐይ በታች በሚደክምበት ድካም ሁሉ የሰው ትርፉ ምንድር ነው?

5) ሕይወት ፈታኝ ናት

● 1ዮሐ.2÷15-16

15-ዓለምን ወይም የዓለምን ነገር ሁሉ አትውደዱ፡፡ ዓለምን የሚወድ እግዚአብሔር አብን አይወድም፡፡

16-በዓለም ያለው ሁሉ የሥጋ ምኞት፣ የዐይን አምሮት፣ የኑሮ ትምክሕት ከዓለም ነው እንጂ ከእግዚአብሔር አብ አይደለም፡፡

በሥጋ ምኞት ፈተና፡- ምግብ፣ ዝሙት፣ ዕቃዎች፣ ገንዘብ፣ ወዘተ . . . በማሳየት ዘወትር ይፈትናል፡፡

② በዓይን ምኞት ፈተና፡- ③ በኑሮ ትምክት ፈተና፡- የስልጣን ምኞት፣ ወዘተ . . . ዘወትር ይፈትናል፡፡ ዓለም የሚሰጠው ነገር የውሸት ደስታ ነው፡፡

3. ወደ ኢየሱስ የመጣ ሰው እውነተኛ ዕረፍትና ሰላም ያገኛል፡፡

1) በእምነቱ በነፃነት ይኖራል፡፡

● ዮሐ.8÷32 32. እውነትን ታውቃላችሁ፣ እውነትም እናንተን ነጻ ያወጣችኋል፡፡”

2) በዓለም በማይወሰድ ሰላምና ዕረፍት ውስጥ ይኖራል፡፡

● ዮሐ.14÷27

27. “ሰላምን እተውላችኋለሁ፣ ሰላሜንም እሰጣችኋለሁ፣ እኔ የምሰጣችሁ ሰላም ዓለም እንደሚሰጠው ዐይነት አይደለም፣ ልባችሁ አይጨነቅ፣ ደግሞም አይፍራ፡፡

3) በእውነተኛ ፍቅርና በዘላለም ሕይወት ውስጥ ይኖራል፡፡

● ሮሜ.8÷38-39

38. ይህን ተረድቻለሁ፤ ሞትም ይሁን ሕይወት፣ መላእክትም ይሁኑ አጋንንት፣ ያለውም ይሁን የሚመጣው፣ ወይም ማንኛውም ኀይል፤

39. ከፍታም ይሁን ጥልቀት፣ ወይም የትኛውም ፍጥረት፣ በጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ካለው ከእግዚአብሔር ፍቅር ሊለየን አይችልም፡፡

4) የተረጋጋ ሕይወትና የሚያድግ ፀባይ ይቀበላል፡፡ የተፅናና ሰው ሌላውን ያበረታታል፤ ሕይወቱ የተረጋጋ ሰው ሌላውን ያረጋጋ፤ በሕይወቱ እርካታና ምስጋና የሌለ ሰው ያ ሰው የተጎዳ ሰው ነው፡፡

● ፊልጵ.4÷13 13-ኃይልን በሚሰጠኝ በክርስቶስ ሁሉን እችላለሁ።

4. ኢየሱስ ክርስቶስ ማን ነው?

1) ኃጢአታችንን የሚያስተሰርይና አዳኛችን ነው፡፡

● ማቴ.1÷21

21-ማርያም ወንድ ልጅ ትወልዳለች፤ ስሙንም ኢየሱስ ብለህ ትጠራዋለህ፣ እርሱ ሕዝቡን ከኃጢአታቸው ያድናቸዋልና፡፡”

2) ሕይወታችን ነው፡፡

● 1ዮሐ.5÷11-12

11-ምስክርነቱም እግዚአብሔር የዘለዓለም ሕይወት እንደ ሰጠንና ይህም ሕይወት በልጁ እንዳለ የማመሰክር ነው፡፡

12-የእግዚአብሔር ልጅ ያለው ሕይወት አለው፡፡ የእግዚአብሔር ልጅ የሌለው ግን ሕይወት የለውም፡፡

3) ፈራጅና ዳኛ ነው፡፡

● 2ቆሮ.5÷10

10-እያንዳንዱ በምድራዊ ሕይወቱ ላደረገው ክፉም ሆነ ደግ ነገር እንደየሥራው ዋጋውን ለመቀበል ሁላችንም በክርስቶስ የፍርድ ወንበር ፊት መቅረብ አለብን፡፡

4) ኢየሱስ ማለት ክርስቶስ (መሲህ፣ ንጉስ፣ ካህን) ሆኖ የእግዚአብሔር ልጅ ነው፡፡

● ማቴ.16÷16 16. ስምዖን ጴጥሮስም፣ “አንተ ክርስቶስ የሕያው እግዚአብሔር ልጅ ነህ” ሲል መለሰ፡፡

★ ኢየሱስ አሁን የሚያደርገውን ሥራ

① ነፍስን ከኃጢአት ነፃ ያወጣል፡፡ ② የሰይጣንን ፈተና ያሸንፋል፡፡

ስለሰው እግዚአብሔርን በየቀኑ ይማልዳል፡፡

5. ክርስቲያኖች በኢየሱስ ክርስቶስ በኩል በአስገራሚ በረከት ውስጥ ይኖራሉ፡፡

1) በእውነተኛ ነፃነት ይኖራሉ፡፡ ኢየሱስ የነፍስንና የሥጋን ህመም እንዲሁም ርግማኔን ሁሉ አስወግዶ የኃጢአት ይቅርታ ሰጥተዋል፡፡

● ገላ.5÷1

1-ክርስቶስ ነጻ ያወጣን በነጻነት እንድንኖር ነው፡፡ ስለዚህ ጸንታችሁ ቁሙ፤ እንደገናም በባርነት ቀንበር አትጠመዱ፡፡

2) በአብርሃም በረከት ተባርኮ ይኖራሉ፡፡ የአብርሃም 5ቱ በረከቶች

● ገላ.3÷14

14-ይህም የሆነው እግዚአብሔር ለአብርሃም የሰጠው በረከት በኢየሱስ ክርስቶስ አማካይነት ለአሕዛብ እንዲደርስና እኛም እግዚአብሔር እሰጣችኋለሁ ያለውን መንፈስ ቅዱስን በእምነት እንድንቀበል ነው፡፡

3) በመንፈስ ቅዱስ ተስፋ ይኖራሉ፡፡

የመንፈስ ቅዱስ ምስክርነት፣ ሥልጣን ስላለን፣ መንፈስ ቅዱስ አስተማሪ ይሆናል፡፡

● ገላ.3÷14 14-ይህም የሆነው እግዚአብሔር ለአብርሃም የሰጠው በረከት በኢየሱስ ክርስቶስ አማካይነት ለአሕዛብ እንዲደርስና እኛም እግዚአብሔር እሰጣችኋለሁ ያለውን መንፈስ ቅዱስን በእምነት እንድንቀበል ነው፡፡

4) በእውነተኛ ሥልጣን ይኖራሉ፡፡

● ፊልጵ.4÷13 13-ኃይልን በሚሰጠኝ በክርስቶስ ሁሉን እችላለሁ።

5) ከአሁን ጀምሮ ከኢየሱስ ጋር ተባርከው ይኖራሉ፡፡

● ራዕ.3÷20 20-እነሆ! እኔ በበር ቆሜ አንኳኳለሁ፤ ማንም ድምፄን ሰምቶ በሩን ቢከፍትልኝ ወደ እርሱ ገብቼ ከእርሱ ጋር እበላለሁ፤ እርሱም ከእኔ ጋር ይበላል፤

★ ፀሎት፡- አሁን ኢየሱስን እመን፤ ኢየሱስ ለችግሮችህ ሁሉ መፍትሄን ይሰጣል፡፡

ምዕራፍ አራት

4. የኢየሱስ ክርስቶስ ሚስጥር (ዕብ.4÷14-15)

● ዕብ.4÷14-15

14-እንግዲህ ሰማያትን ዘልቆ ወደ ላይ ወደ ሰማይ የወጣ ታላቅ የካህናት አለቃ ስላለን እምነታችንን አጥብቀን እንያዝ፤ የካህናት አለቃውም የእግዚአብሔር ልጅ ኢየሱስ ነው፡፡

15-እኛ ያለን የካህናት አለቃ በድካማችን ሊራራልን የሚችል ነው፤ እርሱ በሁሉ ነገር እንደ እኛ ተፈተነ፤ ሆኖም ምንም ኃጢአት አልሠራም፡፡

በአሜሪካ አኩለሁማ ዩንቨርስቲ ውስጥ አንድ ሰው ቺንጀሮን በእጅ ምልክት መናገርን እንድችል 140 ቃላቶችን አስተማሪ፡፡ ከዚያ በኋላ በመጀመሪያ የተኛውን ቃል ነው ያወቅኸው? ተብሎ ሲጠየቅ ቺንጀሮ ሲመልስ በእጅ ምልክት "እባክህ እኛን አውጣን" የሚለውን ነው አለ፡፡ እንደዚህም እንስሳት ለመታሰር አይፈልጉም፡፡

ሰው ደግሞ የኃጢአት ባሪያ ለመሆን አይፈልግም፤ ከኃጢአት ችግሮች ተላቅቆ መፍትሄን ለማግኘት ይፈልጋል፡፡ ስለ እኛ ኃጢአት ችግሮች ኢየሱስ ክርስቶስ ብቻውን መፍትሄ ይሰጣል፡፡ ደግሞም እኛን ከኃጢአት እስራት ይፈታል፡፡እውነተኛ ነፃነት በኢየሱስ ክርስቶስና በመንፈስ ቅዱስ ውስጥ ብቻ ይገኛል፡፡ የኃጢአታችን መንፃት ሚስጥር የሆነው ኢየሱስ ክርስቶስ ነው፡፡

★ እግዚአብሔር አብሮን እንዳለ ማረጋገጥ

① በምንፀልይበት ጊዜ መልስን ይሰጣል፡፡

② በምንሠራበት ጊዜ ሰላምን ይሰጣል፡፡

ቤተክርስቲያንን በምናገለግልበት ጊዜ ደስታን ይሰጣል፡፡

ወንጌልን በምንሰብክበት ጊዜ ታምራት ያደርጋል፡፡

ውጤት፡- እግዚአብሔር ምስክርነት ካለው ሰው ጋር አንድ ላይ መኖሩን የሚገልፀው ሰላም፣ ደስታንና ዕረፍት በመስጠት ነው፡፡

1. ያለ ኢየሱስ ክርስቶስ የሚኖሩ ሰዎች

1) በዓለም ከንቱነት ውስጥ ይኖራሉ፡፡

● ኤፌ.2÷2 2-በዚያን ጊዜ የዚህን ዓለም ክፉ አካሄድ ትከተሉ ነበር፤ እንዲሁም በአየር ላይ ያሉትን የመናፍስት ኀይሎች ለሚገዛው ትታዘዙ ነበር፤ እርሱ በማይታዘዙት ሰዎች ላይ የሚሠራ ርኩሱ መንፈስ ነው፡፡

2) ራስን ብቻ በመውደድ ውስጥ ይኖራሉ፡፡

● ቆላ.3÷5 5-ስለዚህ በእናንተ የሚገኙትን የምድራዊ ሕይወት ምኞቶችን ሁሉ ግደሉ፤ እነርሱም፣ "ዝሙት፣ ርኩሰት፣ ፍትወት፣ ክፉ ምኞት፣ ጣዖት ማምለክ የሆነ መጐምጀት" ናቸው፡፡

3) ጣኦትንና ጠንቋይን በማምለክ ነፍሳቸውን ፈጽም በማጥፋት ውስጥ ይኖራሉ፡፡

● ዘፀ.20÷4-5

4-በሰማይም ሆነ በምድር ወይም ከምድር በታች ባለው ውሃ ውስጥ ከሚኖሩት ነገሮች የማንኛውንም ዐይነት ምስል ጣዖት አድርገህ አትሥራ፤

5-እኔ እግዚአብሔር አምላክህ እጅግ ቀናተኛ ስለ ሆንኩ ተቀርጾ የተሠራውን ማንኛውም ጣዖት አታምልክ፤ አትስገድለትም፤ እኔ የሚጠሉኝን ሁሉ እቀጣለሁ፤ ዘራቸውንም ሁሉ እስከ ሦስትና አራት ትውልድ ድረስ እበቀላለሁ፡፡

4) በጭንቀትና ፍርሃት የእምነትን ሰላም ሳያገኙ ይኖራሉ፡፡

● ማቴ.6÷34

34. ስለዚህ ለነገ አትጨነቁ፤ የነገ ሥራ ለነገ ይጨነቃልና ለቀኑ ክፋቱ በቀኑ ይበቃዋል።

5) ከሞት በኃላ ወደ ሲኦል ይሄዳሉ፡፡

● ሉቃ.16÷19-31

19. ደግሞ ኢየሱስ እንዲህ አለ፣ "ሐምራዊና ቀጭን ልብስ የሚለብስ አንድ ሀብታም ሰው ነበር፣ እርሱም በየቀኑ በቅንጦት ይኖር ነበር፡፡

20. በአንጻሩም መላ ሰውነቱ በቊስል የተወረረ አንድ አልዓዛር የሚባል ድኻ በዚህ በሀብታም ሰው ቤት ደጃፍ ተኝቶ ነበር፣

21. አልዓዛር ከሀብታሙ ሰው ማእድ የወደቀውን ፍርፋሪ እንኳ ሊመገብ ይመኝ ነበር፣ ውሾችም እየመጡ ቊስሉን ይልሱ ነበር፡፡

22. ከዚህም በኋላ ድኻው ሰው ሞተ፣ መላእክትም ወደ አብርሃም ዕቅፍ ወሰዱት፣ ሀብታሙም ሰው ደግሞ ሞቶ ተቀበረ፡፡

23. ሀብታሙ ሰው በሲኦል እየተሠቃየ ሳለ፣ ቀና ብሎ ከሩቅ በአብርሃም በዕቅፉ የነበረውን አልዓዛርን አየ፡፡

24. ሀብታሙ ሰው አብርሃምን፣ 'አብርሃም አባት ሆይ፣ ራራልኝ፣ በዚህ በእሳት ነበልባል ውስጥ በብርቱ እሠቃያለሁና አልዓዛር የጣቱን ጫፍ ውሃ ነክሮ ምላሴን እንዲያቀዘቅዝልኝ እባክህ ላክልኝ' እያለ ጮኸ፡፡

25. አብርሃም ግን እንዲህ አለው፣ 'ልጄ ሆይ፣ አንተ በምድራዊ ሕይወትህ ዘመን መልካም ነገሮችን እንደ ተቀበልህ፣ አልዓዛርም ክፉ ነገሮችን እንደ ተቀበለ አስታውስ፣ አሁን ግን አልዓዛርም እዚህ ሲጽናና፣ አንተ በሥቃይ ላይ ትገኛለህ፡፡

26.ከሁሉም በላይ ከዚህ ወደ እናንተ ለማለፍ የሚፈልጉ እንደማይችሉ፣ እዚያ ያሉትም ደግሞ ወደ እኛ እንዳይሻገሩ፣ በእኛና በእናንተ መካከል ትልቅ ገደል ተደርጎአል፡፡

27. ሀበታሙም እንዲህ አለ፣ 'አባት ሆይ፣ እንግዲያውስ እባክህ አልዓዛርን ወደ አባቴ ቤት እንድትልከው እለምንሃለሁ፣

28. ለእኔ አምስት ወንድሞች ስላሉኝ፣ አልዓዛር ሄዶ እነርሱ ወደዚህ የሥቃይ ስፍራ እንዳይመጡ ያስጠንቅቃቸው፡፡

29. አብርሃም ግን እንዲህ አለው፣ 'ለእነርሱ ሙሴና ነቢያት አሏቸው፣ እነርሱን ይስሙ'

30. ሀብታሙም ሰው፣ 'አባት አብርሃም ሆይ፣እንደዚህ አይደለም፤ አንድ ሰው ከሙታን ተነሥቶ ቢሄድላቸው ንስሓ ይገባሉ' አለ፡፡

31. አብርሃምም፣ 'እነርሱ ሙሴንና ነቢያትን የማይሰሙ ከሆነ፣ አንድ ሰው ከሙታን ቢነሣ እንኳ እነርሱ አያምኑም' አለው፡፡

2. እግዚአብሔር በኢየሱስ ክርስቶስ በኩል ነፃ ያወጣል፡፡

1) ከብሉይ ኪዳን ህግ ርግማን ነፃ ያወጣል፡፡ ኢየሱስ ለሚያምኑ ሰዎች ሁሉ ስለ ችግሮቻቸው መፍትሄ ይሰጣል፡፡ አሁን መንፈስ ቅዱስን ተከተል፡፡

● ገላ.3÷13 13-“በእንጨት ላይ ተሰቅሎ የሚሞት ሁሉ የተረገመ ነው” ተብሎ ስለ ተጻፈ ክርስቶስ ስለ እኛ እንደ ተረገመ ሰው ሆኖ ሕግ ከሚያስከትለው ርግማን ዋጀን፡፡

2) ከሁሉ ጠላቶች ነፃ ያወጣል፡፡

● መዝ.136÷24 24-ከጠላቶቻችንም እጅ አድኖናልና ምሕረቱ ለዘላለም ነውና

3) ከፍርስራሽና ከረግረግ ጭቃ ነፃ ያወጣል፡፡

● መዝ.103÷4 4-ሕይወትሽን ከጥፋት የሚያድናት፥ በምሕረቱና በቸርነቱ የሚከልልሽ፥

4) ከሞት ፍርሃት ነፃ ያወጣል፡፡

ኢየሱስን የምናምን እኛ ለዘላለም እንኖራለን፡፡

● ዮሐ.11÷25

25. ኢየሱስም እንዲህ አላት፤ “እኔ ትንሣኤና ሕይወት ነኝ፤ በእኔ የሚያምን ቢሞትም እንኳ በሕይወት ይኖራል፤

5) ከክፉ ትውልድ ነፃ ያወጣል፡፡

● ገላ.1÷4 4-ከዚህ ከክፉ ዘመን ያድነን ዘንድ በአምላካችንና በአባታችን ፈቃድ ክርስቶስ ስለ ኃጢአታችን ራሱን ሰጠ፡፡

3. ካለ ኢየሱስ ክርስቶስ በቀር ከክፉ ነፃ መውጣት አይቻልም

1) በኢየሱስ ክርስቶስ ስም እመን፡፡

● ማቴ.1÷21 21-ማርያም ወንድ ልጅ ትወልዳለች፤ ስሙንም ኢየሱስ ብለህ ትጠራዋለህ፤ እርሱ ሕዝቡን ከኃጢአታቸው ያድናቸዋልና፡፡”

2) አሁን በኢየሱስ ክርስቶስ ተመካ፡፡

● ሮሜ 3÷24 24-ስለዚህ ሰዎች ኢየሱስ ክርስቶስ በፈጸመው በአዳኝነት ሥራ በእግዚአብሔር ጸጋ ብቻ ይጸድቃሉ፡፡

3) የኢየሱስ ክርስቶስ ደም ብቻ ከኃጢአት ያድናል

● ኤፌ.1÷7 7-ከእግዚአብሔር ጸጋ ሙላት የተነሣ በልጁ ደም ተዋጅተን የኃጢአታችንን ይቅርታ አገኘን፡፡

4) ኢየሱስ ክርስቶስ የሰይጣንን ሥልጣን ፈጽም ያፈርሳል፡፡

● ዕብ.2÷14-15 14-እኛ ያለን የካህናት አለቃ በድካማችን ሊራራልን የሚችል ነው፤ እርሱ በሁሉ ነገር እንደ እኛ ተፈተነ፤ ሆኖም ምንም ኃጢአት አልሠራም፡፡

15-እንዲሁም ሞትን በመፍራት ምክንያት ዕድሜ ልካቸውን በባርነት ይገዙ የነበሩትን ለመዋጀት ነው፡፡

5) ኢየሱስ ለሕይወታችን ችግር ሁሉ መፍትሔ መስጠት

● ዮሐ.19÷30 30. ኢየሱስም ሆምጣጤውን ከቀመሰ በኋላ “ተፈጸመ!” አለ፡፡ ራሱን ዘንበል አድርጎም ነፍሱን ሰጠ፡፡

4. ኢየሱስ አሁን አንተን በስምህ ጠርቶ ይፈልገሃል፡፡

1) ሸክም የከበዳቸውንና ደካሞችን ሁሉ ወደ እኔ ኑ ይላቸዋል፡፡ አንተ ልብህን ክፈት

● ማቴ.11÷28 28. እናንተ ደከሞች ሸክማችሁ የከበደ ሁሉ ወደ እኔ ኑ፣ እኔም ለእናንተ ዕረፍት እሰጣችኋለሁ፡፡

2) የልብህን በር መክፈት አለብህ

አሁን ኢየሱስን ለመቀበል ይህ ምቹ ነው፡፡

● ራዕ.3÷20 20-እነሆ! እኔ በበር ቆሜ አንኳኳለሁ፤ ማንም ድምፄን ሰምቶ በሩን ቢከፍትልኝ ወደ እርሱ ገብቼ ከእርሱ ጋር እበላለሁ፤ እርሱም ከእኔ ጋር ይበላል፤

3) ኢየሱስን ስትቀበል የእግዚአብሔር ልጅ የመሆን ልዩ ሥልጣን ትቀበላለህ፡፡

● ዮሐ.1÷12-13 12. ነገር ግን ኢየሱስ ራሱ ለተቀበሉትና በስሙ ላመኑት ሁሉ ሰዎች የእግዚአብሔር ልጆች የመሆን መብት ሰጣቸው፡፡

13. እነርሱም ከእግዚአብሔር ተወለዱ እንጂ ከደም ወይም ከሥጋ ፈቃድ ወይም ከሰው ፈቃድ አልተወለዱም።

4) በተትረፈረፈ ሕይወት ትኖራለህ፤

● ዮሐ.10÷10 10. ሌባው ሊሰርቅ፣ ሊገድልና ሊያጠፋ ብቻ ይመጣል፣ እኔ የመጣሁት በጎቼ ሕይወት እንዲያገኙና የተትረፈረፈ ሕይወት እንዲኖራቸው ነው፡፡

5) በሕይወት ለመኖርና ለመሞት የልብ ውሳኔ ይጠይቃል፤

ደህንነትን ለመምረጥና ሞትን ለመምረጥ የሰው ምርጫ እንደሆነ ስገልጽ [2]ከሁሉም በላይ ልብህን ጠብቅ የሕይወት ምንጭ ነውና[2] ይላል፡፡

● ምሳሌ 4÷23 23-አጥብቀህ ልብህን ጠብቅ፥ የሕይወት መውጫ ከእርሱ ነውና።

5. በኢየሱስ ስም ማመንህን በምስክርነት ግለፅ

1) ከጠንቋይና ከጣኦት አምልኮ ለዘላለም መውጠትህን መስክር።

● ሮሜ 8÷2 2-በኢየሱስ ክርስቶስ የሚገኘውን ሕይወት የሚሰጥ የመንፈስ ቅዱስ ሕግ ከኃጢአትና ከሞት ሕግ ነጻ አውጥቶኛል፡፡

2) መንፈስ ቅዱስ በአንተ ውስጥ መኖሩንና ሁልጊዜ እየመጣ ማጽናናቱን መስክር

● ዮሐ.14÷16 16. እኔ አብን እለምናለሁ፣ እርሱም ከእናንተ ጋር ለዘላለም የሚኖር ሌላ አጽናኝ ይሰጣችኋል፣

3) ሰማያዊውን ሰላምና ዕረፍት አጊኛትህን ግለፅ

እግዚአብሔር የመኖሩን ማረጋገጫ በምንፀልይበት ጊዜ እርሱ ይሰጣናል፡፡

● ዮሐ.14÷27

27. “ሰላምን እተውላችኋለሁ፣ ሰላሜንም እሰጣችኋለሁ፣ እኔ የምሰጣችሁ ሰላም ዓለም እንደሚሰጠው ዐይነት አይደለም፣ ልባችሁ አይጨነቅ፣ ደግሞም አይፍራ፡፡

● **ኤር**.33÷3 3-**ወደ እኔ ጩኽ፥ እኔም እመልስልሃለሁ አንተም የማታውቀውን ታላቅና ኃይለኛ ነገርን አሳይሃለሁ።**

4) **በፀሎት መልስ ማግኘትህን መስክር፡፡**

● **ዮሐ**.16÷24 24. **እስከ አሁን እናንተ በስሜ ምንም ነገር አለመናችሁም፣ ለምኑ ይሰጣችኋል፣ ደስታችሁም ፍጹም ይሆናል፡፡**

5) **ለዓለም ወሳኝ ሰው መሆንህን መስክር፡፡**

● **ማቴ**.28÷18-20

18-**ኢየሱስ ወደ ደቀ መዛሙርቱ ቀረበና እንዲህ አላቸው፣** “**ሥልጣን ሁሉ በሰማይና በምድር ተሰጥቶኛል፣**

19-**ስለዚህ እናንተ ወደ ዓለም ሕዝብ ሁሉ ሂዱ፣ በአብ፣ በወልድና በመንፈስ ቅዱስ ስም እያጠመቃችኋቸው የእኔ ደቀ መዛሙርት አድርጉአቸው፡፡**

20-**እኔ ለእናንተ ያዘዝኋችሁን ሁሉ እንዲጠብቁ አስተምሯቸው፣ እነሆ፣ እኔም እስከ ዓለም መጨረሻ ድረስ ሁልጊዜ ከእናንተ ጋር ነኝ፡፡**”

ምዕራፍ አምስት

5. የኢየሱስ ስም ስልጣናትንና ኃይላትን ያሸንፋል

● ማቴ.28÷18

18-ኢየሱስ ወደ ደቀ መዛሙርቱ ቀረበና እንዲህ አላቸው፣ “ሥልጣን ሁሉ በሰማይና በምድር ተሰጥቶኛል፣

ሕይወት ሁልጊዜ በጦርነት ውስጥ ትኖራለች፡፡ በዓለም በማንኛውም ሥፍራ ጦርነት አለ፤ የራሱን ድንበር የማስጠበቅ ጦርነት፣ የፓለቲካ ጦርነት፣ የኢኮኖሚ ጦርነት፣ የትምህርት ቤት ጦርነት፣ የትራፊክ ጦርነት ወዘተ . . . እኛ በማያቋርጥ ጦርነቶች ውስጥ እንኖራለን፡፡ እኛ ለሕይወታችን የሚበልጠውን ታላቅ ጦርነት መዋጋት ያስፈልጋል፡፡ ይህም ጦርነት መንፈሳዊ ጦርነት ነው፡፡ እኛ ይህን መንፈሳዊ ጦርነት በፍፁም የምናሸንፍ ሰዎች ልንሆን ይገባል፡፡ ለሁሉም ጦርነቶች አሸናፊና ተሸናፊ አለ፡፡ ለአሸናፊ ሰው በረከትና ስጦታ ይሰጣዋል፡፡ ነገር ግን ለተሸነፈ ሰው ምንም የሚሰጥ ነገር የለውም፤ ሀፍረትንና ውድቀት ብቻ ይላከሳል፡፡ እግር ኳስ ተጫውተው ያሸነፉ ክለብ (ቡድን) በጣም ይደሰታል፡፡ እንደዚህም መንፈሳዊ ጦርነት ስናሸንፍ ደስታና ሰላም ይኖራል፡፡ የአሸናፊነት ምስጢር ምንድን ነው?

★ የክርስቲያን ሕይወት መውደቅ ምክንያት ምንድን ነው?

① የእግዚአብሔርን ቃል መጠርጠር ነው:: የእግዚአብሔርን ቃል አለመታዘዝ::

② የእግዚአብሔርን ፀጋ አለመፈለግ።

③ የመንፈስ ቅዱስን ሥራ አልመቀበል።

④ ራሴ የእግዚአብሔር ልጅ መሆኔን አለማወቅ። ስለዚህ የኢየሱስን ስም አለመወደድ።

a. የኢየሱስን ስም አለመጠቀም።

b. የኢየሱስን ስም አለማመን።

c. የራሴ ሥልጣንና ልምምድ ብቻ መከሉል።

ውጤት - የወንጌልን ሥልጣን በኢየሱስ ስም መግለጥ።

በመጀመሪያ እግዚአብሔር የተወው ሰው ምን ዓይነት ቅርፅ አለው?

1) ሰው በመጀመሪያ በእግዚአብሔር መልክ ተፈጥሯል፡፡

● ዘፍ.1÷27

27-በዚህ ዐይነት እግዚአብሔር ሰውን በራሱ መልክ ፈጠረ፤ በእግዚአብሔር መልክ ፈጠረው፤ ወንድና ሴት አድርጎም ፈጠራቸው፡፡

2) ሰይጣን አታልሎ የእግዚአብሔርን መልክና ሥልጣን ከሰዎች ወሰደ፡፡ ሰይጣን የሕይወታችን ሌባ ነው፡፡

● ዘፍ.3÷1-10

1-እግዚአብሔር አምላክ ከፈጠራቸው አራዊት ሁሉ፣ እባብ እጅግ ተንኰለኛ ነበረ፤ ስለዚህ እባብ “በአትክልቱ ቦታ ካሉት ዛፎች ሁሉ ፍሬ እንዳትበሉ በእርግጥ እግዚአብሔር አዞአችኋልን?” ሲል ሴቲቱን ጠየቃት፡፡

2-ሴቲቱም “በአትክልት ቦታ ካሉት ዛፎች ፍሬ ልንበላ እንችላለን፤

3-ነገር ግን እግዚአብሔር ‘በአትክልቱ ቦታ ካለው ዛፍ ፍሬ አትብሉ፤ በእጃችሁም አትንኩት፤ ይህን ብታደርጉ ትሞታላችሁ’ ብሎ አስጠንቅቆናል” ስትል መለሰችለት፡፡

4-እባቡም እንዲህ አላት፡- “በፍጹም አትሞቱም፤

5-እግዚአብሔር ይህን ያዘዛችሁ ከዚያ ዛፍ ፍሬ በበላችሁ ጊዜ እንደ እግዚአብሔር እንደምትሆኑና ደጉን ከክፉ ለይታችሁ እንደምታውቁ ስለሚያውቅ ነው፤”

6-ሴቲቱም ዛፉ የሚያምር፣ ፍሬውም ለመብላት የሚያስጐመጅና ጥበብን የማያስገኝ እንደ ሆነ ባየች ጊዜ ከፍሬው ወስዳ በላች፤ ለባሏም ከፍሬው ሰጠችው፤ እርሱም በላ፡፡

7-የሁለቱም ዐይኖች ተከፍተው እራቁታቸውን እንደ ሆኑ ተገነዘቡ፤ ስለዚህ የበለስ ቅጠሎችን አገናኝተው ሰፉና ገልድማው እርቃናቸውን ሸፈኑ፡፡

8-በመሸ ጊዜ፣ እግዚአብሔር አምላክ በአትክልቱ ቦታ ውስጥ ሲመላለስ ድምፁን ሰሙ፤ አዳምና ሚስቱ እግዚአብሔር አምላክ እንዳያያቸው በዛፎች መካከል ተደበቁ፡፡

9-ነገር ግን እግዚአብሔር አምላክ አዳምን ጠርቶ “የት ነው ያለኸው?” ሲል ጠየቀው፡፡

10-አዳምም “በአትክልቱ ቦታ ውስጥ የአንተን ድምፅ ሰማሁ፤ እራቁቴንም ስለ ሆንኩ በመፍራት ተደበቅሁ” አለ፡፡

3) በዚህ ጊዜ ውድቀትና ህመም ሞት ወደ ሰዎች መጣ፡፡

● ዘፍ.3÷16-19

16-ሴቲቱንም፣ “በእርግዝናሽ ወራት ጭንቀትሽን፣ በምትወልጂበትም ጊዜ የምጥ ሥቃይሽን አበዛሁ፤ ይህም ሁሉ ሆኖ ፍላጎትሽ ለባልሽ ይሆናል፡፡ ለእርሱም ታዛዥ ትሆኚአለሽ” አላት፡፡

17-አዳምንም እንዲህ አለው፣ “የሚስትህን ቃል ሰምተህ ‘አትብላ’ ያልኩህን ፍሬ ከዛፉ ወስደህ ስለ በላህ፣ አንተ በፈጸምከው ክፉ ሥራ ምክንያት ምድር የተረገመች ትሁን፤ በሕይወት ዘመንህ ሁሉ ምግብህን ከእርስዋ የምትበላው በብርቱ ድካም ነው፡፡

18-ምድር እሾኽና አሜከላ ታበቅላለች፤ አንተም የዱር ተክሎችን ትበላለህ፡፡

19-ወደ መጣህበት ወደ መሬት እስክትመለስ ድረስ፣ እንጀራህን በግንባርህ ላብ ትበላለህ፡፡” ዐፈር ነህና፣ ወደ ዐፈርም ትመለሳለህ፡፡

4) ጣኦትንና ጠንቋይን በማምለክ በሰይጣን ባሪያ ውስጥ ይኖራል፡፡ ነገር ግን ኢየሱስ ክርስቶስን የሚያምን ሰው ከዚህ ይተርፋል፡፡

ምሳሌ፡- አንድ ሰው ኢየሱስ ክርስቶስን ከማመኑ በፊት የሚያየው ምስል ይኖራል፤ ነገር ግን ኢየሱስ ክርስቶስን ካመነ በኋላ የመጀመሪያውን ምስልና አሁን ያለበትን ሁኔታ ሲያነፃፅር በጣም ይቀየራል፡፡ ምስል የነበረው ቀርቶ በመንፈሳዊ ዓይን ማየት ይጀምራል፡፡

● ኤፌ.2÷2-3

2-በዚያን ጊዜ የዚህን ዓለም ክፉ አካሄድ ትከተሉ ነበር፤ እንዲሁም በአየር ላይ ያሉትን የመናፍስት ኀይሎች ለሚገዛው ትታዘዙ ነበር፤ እርሱ በማይታዘዙት ሰዎች ላይ የሚሠራ ርኩሱ መንፈስ ነው፡፡

3-እኛም ሁላችን ከዚህ በፊት በእነርሱ መካከል የሥጋችንን ፈቃድና የአእምሮአችንን ሐሳብ እየተከተልን በሥጋችን ምኞት እንኖር ነበር፤ እንደ ሌሎቹም በተፈጥሮአችን በእግዚአብሔር ቍጣ ሥር ነበርን፡፡

5) በራሱ ሥልጣን ከቶ መውጣት አይችልም፡፡

● ኤፌ.2÷1

1-እናንተ በበደላችሁና በኃጢአታችሁ ምክንያት በመንፈሳዊ ኑሮአችሁ የሞታችሁ ነበራችሁ፤

6) ከሞት በኋላ ወደ ሲኦል ለዘላለም ወደ ማይጠፋ እሳት ውስጥ ይገባል፡፡

● ራዕ.21÷8

8-ነገር ግን ፈሪዎች፣ እመነት ቢሶች፣ ርኩሶች፣ ነፍሰ ገዳዮች፣ አመንዝሮች፣ አስማተኞች፣ ጣዖት አምላኪዎች ውሸታሞች ሁሉ ዕጣ ክፍላቸው በዲን በሚቃጠለው በእሳት ባሕር ውስጥ ይሆናል፤ ይህ ሁለተኛው ሞት ነው፡፡"

7) ይህንን ቅርፅና ሥልጣን እንደገና ለመመለስ ኢየሱስ መጣ፡፡

● 1ዮሐ.3÷8

8-ዲያብሎስ ከመጀመሪያው አንሥቶ ኃጢአት ስለሚሠራ ኃጢአትን የሚሠራ ሁሉ የዲያብሎስ ወገን ነው፡፡ የእግዚአብሔር ልጅ የተገለጠውም የዲያብሎስን ሥራ ለማፍረስ ነው፡፡

8) ኢየሱስን ለተቀበሉት ሁሉ ለችግሮቻቸው መፍትሄንና ሥልጣንን እንደገና ይመልሳል፡፡

● ዮሐ.1÷12

12. ነገር ግን ኢየሱስ ራሱ ለተቀበሉትና በስሙ ላመኑት ሁሉ ሰዎች የእግዚአብሔር ልጆች የመሆን መብት ሰጣቸው፡፡

የኢየሱስ ስም ሥልጣናትንና ኃይላትን ያሸንፋል፡፡

1) ኢየሱስ በሰማይና በምድር ያሉትን ሥልጣን ሁሉ የያዘ ጌታ ነው፡፡

● ማቴ.28÷18-20

18-ኢየሱስ ወደ ደቀ መዛሙርቱ ቀረበና እንዲህ አላቸው፣ "ሥልጣን ሁሉ በሰማይና በምድር ተሰጥቶኛል፤

19-ስለዚህ እናንተ ወደ ዓለም ሕዝብ ሁሉ ሂዱ፣ በአብ፣ በወልድና በመንፈስ ቅዱስ ስም እያጠመቃችኋቸው የእኔ ደቀ መዛሙርት አድርጉአቸው፡፡

20-እኔ ለእናንተ ያዘዝኋችሁን ሁሉ እንዲጠብቁ አስተምሯቸው፣ እነሆ፣ እኔም እስከ ዓለም መጨረሻ ድረስ ሁልጊዜ ከእናንተ ጋር ነኝ፡፡"

2) ኢየሱስ የሰይጣንን ሥራ አፍርሶ ነፃ ያወጣል፡፡

● 1ዮሐ.3÷8

8-ዲያብሎስ ከመጀመሪያው አንሥቶ ኃጢአት ስለሚሠራ ኃጢአትን የሚሠራ ሁሉ የዲያብሎስ ወገን ነው፡፡ የእግዚአብሔር ልጅ የተገለጠውም የዲያብሎስን ሥራ ለማፍረስ ነው፡፡

3) ኢየሱስ በመስቀል ላይ ሰይጣንን ፈጽም አሸነፈዋል፡፡

● ቆላ.2÷13-15

13-ኃጢአት በመሥራታችሁና ኃጢአተኛ ሥጋችሁ በክርስቶስ በማመን ባለመገረዙ ምክንያት ሙታን ነበራችሁ፤ አሁን ግን እግዚአብሔር ከክርስቶስ ጋር ሕያዋን አድርጓችኋል፤ ኃጢአታችሁንም ሁሉ ይቅር ብሎላችኋል፡፡

14-እርሱ ያንን ይከሰንና ይቃወመን የነበረውን በሕግ ያለውን የዕዳ ጽሑፍ ደመሰሰው፤ በመስቀል ላይ ቸንክሮም ከእኛ አስወገደው፡፡

15-ኀይለትንና ባለሥልጣናትን በመስቀሉ ድል ነሥቶ ትጥቃቸውን ካስፈታ በኋላ ምርኮኞች ሆነው በይፋ እንዲታዩ አደረጋቸው፡፡

4) ኢየሱስ የሚያምኑትን ሰዎች ከጨለማ ሥልጣን ነፃ ያወጣቸዋል፡፡

● ቆላ.1÷13

13-እርሱ ከጨለማ ኀይል አውኛተው ወደ ተወደደው ልጁ መንግሥት እንድንገባ አድርጎናል፡፡

5) ኢየሱስን የሚያምኑት በእውነተኛ ነፃነትና ሰላም ይኖራሉ፡፡

● ሐዋ.10÷38

38-እግዚአብሔር የናዝሬቱን ኢየሱስ በመንፈስ ቅዱስና በኀይል ቀባው፤ ኢየሱስ መልካም ነገርን እያደረገ በዲያብሎስ የተያዙትን ሁሉ ፈወሰ፤ እግዚአብሔርም ከኢየሱስ ጋር ነበረ፡፡

6) ክርስቲያኖች ብንፀልይ እግዚአብሔር እርዳታውን ይሰጣል፡፡

● ዮሐ.16÷24

24. እስከ አሁን እናንተ በስሜ ምንም ነገር አለመናችሁም፣ ለምኑ ይሰጣችኋል፣ ደስታችሁም ፍጹም ይሆናል፡፡

የዚህ ሥልጣን ዋስትና ምንድን ነው?

1) በእኛ ውስጥ መንፈስ ቅዱስ መላኩ ነው፡፡

● ዮሐ.14÷16

16. እኔ አብን እለምናለሁ፣ እርሱም ከእናንተ ጋር ለዘላለም የሚኖር ሌላ አጽናኝ ይሰጣችኋል፣

2) መንፈስ ቅዱስ አስተማሪ መሆኑ ነው፡፡ መንፈስ ቅዱስ በእኛ ውስጥ መኖሩ እንድናስተውል ያደርጋል፡፡

● ዮሐ.14÷16-27

16. እኔ አብን እለምናለሁ፣ እርሱም ከእናንተ ጋር ለዘላለም የሚኖር ሌላ አጽናኝ ይሰጣችኋል፣

17. እርሱም የእውነት መንፈስ ነው፣ ዓለም እርሱን ስለማያየውና ስለማያውቀው ሊቀበለው አይችልም፡፡ እናንተ ግን፣ እርሱ ከእናንተ ጋር ስለሚኖርና በውስጣችሁ ስላለ ታውቁታላችሁ፡፡

18. እኔ ወላጅ እንደሌላቸው ልጆች አልተዋችሁም፣ ተመልሼ ወደ እናንተ እመጣለሁ፡፡

19. ከጥቂት ጊዜ በኋላ፣ ዓለም ከቶ አያየኝም፣ እናንተ ግን ታዩኛላችሁ፡፡ እኔ ሕያው ስለ ሆንሁ እናንተም ሕያዋን ትሆናላችሁ፡፡

20. እኔ በአብ እንዳለሁ፣ እናንተም በእኔ እንዳላችሁ፣ እኔም በእናንተ እንዳለሁ በዚያን ቀን ታውቃላችሁ፡፡

21. እኔን የሚወደኝ ትእዛዜን ተቀብሎ የሚጠብቅ ነው፣ የሚወደኝን አባቴ ይወደዋል፣ እኔም እወደዋለሁ፣ ራሴንም እገልጥለታለሁ፡፡"

22. አስቆሮታዊው ሳይሆን ሌላው ይሁዳ፣ "ጌታ ሆይ! ራስህን ለዓለም ሳይሆን ለእኛ የምትገልጠው እንዴት ነው?" አለው፡፡

23. ኢየሱስ እንዲህ ሲል መለሰለት፣ “እኔን የሚወደኝ ቃሌን ይጠብቃል፣ አባቴም ይወደዋል፣ እኛም ወደ እርሱ መጥተን ከእርሱ ጋር አብረን እንኖራለን፡፡

24. እኔን የማይወደኝ ቃሌን አይጠብቅም፣ እናንተ ይህ የምትሰሙት ቃል የላከኝ የአብ ነው እንጂ የእኔ አይደለም፡፡

25. “አሁን ከእናንተም ጋር እያለሁ ይህን ነገር ነግሬአችኋለሁ፣

26. አብ በእኔ ስም የሚልከው አጽናኙ መንፈስ ቅዱስ ግን ሁሉን ነገር ያስተምራችኋለሁ፣ እኔ የነገርኳችሁንም ሁሉ እንድታስታውሱ ያደርጋችኋል፡፡

27. “ሰላምን እተውላችኋለሁ፣ ሰላሜንም እሰጣችኋለሁ፣ እኔ የምሰጣችሁ ሰላም ዓለም እንደሚሰጠው ዐይነት አይደለም፣ ልባችሁ አይጨነቅ፣ ደግሞም አይፍራ፡፡

3) መንፈስ ቅዱስ ሥልጣናትን ሁሉ እንድናሸንፍ ያደርጋል፡፡

● ማቴ.12÷28-29

28. ነገር ግን እኔ በእግዚአብሔር መንፈስ አጋንንትን የማስወጣ ከሆነ፣ እንግዲህ የእግዚአብሔር መንግሥት በእናንተ ላይ መጥታለች ማለት ነው፡፡

29. ደግሞስ አንድ ሰው አስቀድሞ ኀይለኛውን ሳያስር ወደ ኀይለኛው ቤት ገብቶ ንብረቱን መዝረፍ እንዴት ይችላል? ኀይለኛውን ካሰረው በኋላ ቤቱን መበዝበዝ ይችላል፡፡

4) መንፈስ ቅዱስ በሌሎች አገሮች በሰላም እንድንኖር በማድረጉ

● ሐዋ.1÷8

8-ነገር ግን መንፈስ ቅዱስ በእናንተ ላይ በወረደ ጊዜ ኀይልን ትቀበላላችሁ፤ በኢየሩሳሌም፣ በይሁዳ ምድር ሁሉ፣ በሰማርያ፣ እስከ ምድርም ዳርቻ ድረስ ምስክሮቼ ትሆናላችሁ፡፡”

የኢየሱስን ስም በማመን መመካት

1) ወደ እግዚአብሔር በምንፀልይበት ጊዜ የመልስ በረከትን ስለሚሰጥ

● ዮሐ.14÷13-14

13. አብ በወልድ እንዲከብር፣ በስሜ የምትለምኑትን ሁሉ አደርገዋለሁ፣

14. እናንተ ማንኛውን ነገር በስሜ ብትለምኑኝ፣ እኔ አደርገዋለሁ፡፡

2) በኢየሱስ ስም ለሚያምኑ ሰዎች ሥልጣንና ኃይል ስለሚሰጥ

● ማር.16÷17-18

17. የሚያምኑት እነዚህን ምልክቶች ያደርጋሉ፣ በስሜ አጋንንትን ያወጣሉ፣ በአዲስ ልሳንም ይናገራሉ፣

18. እባቦችን ቢይዙ፣ ወይም የሚገድል መርዝ እንኳ ቢጠጡ አይጐዳቸውም፣ እጃቸውን በበሽተኞች ላይ ሲጭኑ በሽተኞቹ ይድናሉ፡፡”

3) የሰይጣንን ብርቱ ሰፈር ስለሚያፈርስ፡፡

● ሉቃ.10÷19

19. እነሆ! እኔ ለእናንተ እባብንና ጊንጥን እንድትረግጡ፣ የጠላትንም ኀይል ሁሉ እንድትቋቋሙ ሥልጣን ሰጥቻችኋለሁ፣ እናንተን የሚጐዳችሁ ምንም ነገር የለም፡፡

4) በአምልኮና በዝማሬ ለእግዚአብሔር ክብር ይሰጣል።

● ዮሐ.4÷24

24. እግዚአብሔር መንፈስ ነው፣ ለእግዚአብሔር የሚሰግዱለትም በመንፈስና በእውነት ሊሰግዱለት ይገባቸዋል፡፡

5) የኢየሱስ ሕይወት በየቀኑ የደስታ ምንጭ ስለሚሆን።

● ዮሐ.4÷14

14. ነገር ግን እኔ ከምሰጠው ውሃ የሚጠጣ ለዘለዓለም ከቶ አይጠማም፣ እኔ የምሰጠው ውሃ በእርሱ ውስጥ ለዘለዓለም ሕይወት የሚፈልቅ የውሃ ምንጭ ይሆናል፡፡”

6) በኢየሱስ ስም ተፈጥሮን ሁሉ ስለምንቆጣጥር

● ማቴ.28÷18

18-ኢየሱስ ወደ ደቀ መዛሙርቱ ቀረበና እንዲህ አላቸው፣ “ሥልጣን ሁሉ በሰማይና በምድር ተሰጥቶኛል፣

7) **የኢየሱስ መስካሪ ሆነን ዓለምን ስለምናሸንፍ**

- **ሐዋ**.1÷8

8-**ነገር ግን መንፈስ ቅዱስ በእናንተ ላይ በወረደ ጊዜ ኀይልን ትቀበላላችሁ፤ በኢየሩሳሌም፣ በይሁዳ ምድር ሁሉ፣ በሰማርያ፣ እስከ ምድርም ዳርቻ ድረስ ምስክሮቼ ትሆናላችሁ፡፡**”

ምዕራፍ ስድስት

6. የኢየሱስ ክርስቶስ ስም አውቀሃል? (ዮሐ.14÷6-10)

● ዮሐ.14÷6-10

6. ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰለት፣ "እኔ መንገድና እውነት ሕይወትም ነኝ፤ በእኔ በኩል ካልሆነ በቀር ማንም ወደ አብ የሚመጣ የለም፡፡

7. እናንተ እኔን ብታውቁኝ ኖሮ አባቴንም ባወቃችሁት ነበር፡፡ ከአሁን ጅምሮ እናንተ አባቴን ታውቁታላችሁ፣ አይታችሁታልም፡፡"

8. ፊልጶስም፣ "ጌታ ሆይ፣ አብን አሳየንና ይበቃናል" አለው፡፡

9. ኢየሱስም እንዲህ አለው፣ "አንተ ፊልጶስ! ይህን ያህል ጊዜ ከእናንተ ጋር ስኖር አታውቀኝምን? እኔን ያየ አብን እይቶአል፣ እንዴትስ፣ 'አብን አሳየን' ትላለህ?

10. እኔ በአብ እንዳለሁ፣ አብም በእኔ እንዳለ አታምንምን? ለእናንተ የምናገረውን ቃል የምናገረው በራሴ ቃል አይደለም፣ ነገር ግን ሥራውን ሁሉ የሚሠራው፣ በእኔ የሚኖረው አብ ነው፡፡

መልካም ሥራ በመሥራት ወደ መንግሥተ ሰማይ መግባት ይቻላል ብሎ የምያምኑ ሰዎች አሉ፤ ይህንን ሃይማኖት የሚያምኑ ሰዎች በገንዘብ በዕቃዎች (በንብረቶች) ድኻ ሰዎችን ይረዳሉ፡፡ ነገር ግን ስለራሳቸው ኃጢአት መፍትሄን ሳያገኙ በየቀኑ ኃጢአት እየጨመሩ ይሄዳሉ፡፡ ስለዚህ እነርሱ በኃጢአት ውድቀትና በችግር ውስጥ ይኖራሉ፡፡

እኛን ወደ ዘላለም መንገድ ማን ይመራል?

መጽሐፍ ቅዱስ ለዚህ ጥያቄ መፍትሄን ይሰጣል፡፡ ዮሐ.14÷6፡- ኢየሱስም እንዲህ አለው [2]መንገዱ እኔ ነኝ እውነትና ሕይወትም እኔው ነኝ በእኔ በኩል ካልሆነ በቀር ወደ አብ የሚመጣ የለም፡፡[2] ኢየሱስ እውነት፣ መንገድና ህይወት መሆኑን ራሱ ይናገራል፡፡ ኢየሱስ ክርስቶስ ማን ነው?

1. የትኛው ነው ከእነዚህ መከከል ኢየሱስን በትክክል የማያውቀው

1) ከ4ቱ መንፈሳዊውያን ሰዎች አንዱ ያውቃል፡፡

የቡድዝም ሃይማኖት የመሰረተው ሶቀጋ (sokga)፣ ጎበጃ በቻይና አገር አንድ ሃይማኖት (confycianisma)፣

የሙስሊምን ሃይማኖት የመሰረተው መሀመድና፤ የኢየሱስ ክርስቶስ ተከታዩኝ(የኢየሱስ እምናት)

2) የሕዝብ መሪ

3) እጅግ በጣም ጥሩ የሃይማኖት ሰው

4) ያንተ ዓይኖች ኢየሱስ ክርስቶስን እንዴት አዩ?

- ወደ ክፍት ስብሰባ አዲስ ሰው ሲመጣ ጠይቅ፡፡ አንተ /አንቺ /እናንተ/ እርስዎ ኢየሱስ ማን እንደሆነ ያስባሉ? በል።

2. ኢየሱስ ክርስቶስ ማን ነው?

1) የሰዎችን ኃጢአትና ርግማን የሚያስወግድ አዳኝ ነው፡፡

● ማቴ.1÷21

21-ማርያም ወንድ ልጅ ትወልዳለች፤ ስሙንም ኢየሱስ ብለህ ትጠራዋለህ፣ እርሱ ሕዝቡን ከኃጢአታቸው ያድናቸዋልና፡፡”

2) በትንቢት የተነገረው መሲህ ነው፡፡

● ዘፍ.3÷15

15-በአንተና በሴቲቱ መካከል፣ በአንተ ዘርግ በእርስዋ ዘር መካከል ጠላትነት እንዲኖር አደርጋለሁ፡፡ የእርስዋ ዘር የአንተን ራስ ይቀጠቅጣል፤ አንተም የእርስዋን ዘር ተረከዝ ትነክሳለህ፡፡”

3) ሕይወታችን ነው፡፡

● 1ዮሐ.5÷11-12

11-ምስክርነቱም እግዚአብሔር የዘለዓለም ሕይወት እንደ ሰጠንና ይህም ሕይወት በልጁ እንዳለ የሚመሰክር ነው፡፡

12-የእግዚአብሔር ልጅ ያለው ሕይወት አለው፡፡ የእግዚአብሔር ልጅ የሌለው ግን ሕይወት የለውም፡፡

4) ለችግረኞች የሚፈርድ ዳኛ ነው፡፡ ኢየሱስ በፈጽም የሚፈርድ ዳኛ (ፈራጅ) ነው፡፡

● 1ቆሮ.5÷10

10-ይህንንም ስል በአጠቃላይ ከዚህ ዓለም አመንዝራዎች ወይም ከስግብግብ ግለሰቦች ወይም ከሌቦች ወይም ከጣዖት አምላኪዎች ጋር አትተባበሩ ማለቴ አይደለም፤ እንዲህማ ከሆነ ከዓለም መውጣት ያስፈልጋችሁ ነበር ማለት ነው፡፡

● ራዕ.20÷11-15

11-ከዚህ በኋላ ታላቅ ነጭ ዙፋንና በዙፋኑም ላይ የተቀመጠውን አየሁ፤ ምድርና ሰማይ ከፊቱ ሸሹ፤ ስፍራም አልተገኘላቸውም፤

12-ታናናሾችንና ታላላቆችን ሙታን በዙፋኑ ፊት ቆመው አየሁ፤ መጻሕፍትም ተከፈቱ፤ የሕይወት መጽሐፍ የሆነ ሌላ መጽሐፍም ተከፈተ፤ ሙታንም በመጻሕፍቱ ተጽፎ በተገኘው ሥራቸው መሠረት ፍርድ ተቀበሉ፤

13-ባሕርም በውስጡ ያሉትን ሙታን ሰጠ፤ ሞትና ሲኦልም በእነርሱ ውስጥ የነበሩትን ሙታን ሰጡ፤ እያንዳንዱም ሰው በሥራው መሠረት ፍርድ ተቀበለ፡፡

14-ሞትና ሲኦልም ወደ እሳት ባሕር ተጣሉ፤ ይህም የእሳት ባሕር ሁለተኛው ሞት ነው፤

15-ስሙ በሕይወት መጽሐፍ ተጽፎ ያልተገኘ ሁሉ ወደ እሳት ባሕር ተጣለ፡፡

3. ለምን መሲሁ ወደዚህ ዓለም እንዲመጣ እግዚአብሔር አደረገ?

1) በዚህ ዓለም ስለመጣ ነው፡፡

● ሮሜ. 5÷12

12-በአንድ ሰው ምክንያት ኃጢአት ወደ ዓለም ገባ፤ በኃጢአት ምክንያትም ሞት መጣ፤ እንዲሁም ሰው ሁሉ ኃጢአትን ስለ ሠራ ሞት በሰው ሁሉ ላይ መጣ፤

2) ከሞት ሰዎችን ለማስመለጥ

● ዕብ.9÷27

27-ለሰው አንድ ጊዜ መሞት ተመድቦለታል፤ ከሞት በኋላም ፍርድ አለበት፡፡

3) ከብዙ ምኞት ሰዎችን ለማውጣት

● 1 ዮሐ.2÷15-16

15. ዓለምን ወይም የዓለምን ነገር ሁሉ አትውደዱ፡፡ ዓለምን የሚወድ እግዚአብሔር አብን አይወድም፡፡

16. በዓለም ያለው ሁሉ የሥጋ ምኞት፣ የዐይን አምሮት፣ የኑሮ ትምክሕት ከዓለም ነው እንጂ ከእግዚአብሔር አብ አይደለም፡፡

4) ሰዎችን ከዘላለም ሞት ወደ ዘላለም ሕይወት ለማሸጋገር

● ኤፌ.2÷1

1-እናንተ በበደላችሁና በኃጢአታችሁ ምክንያት በመንፈሳዊ ኑሮአችሁ የሞታችሁ ነበራችሁ፤

4. አሁን ኢየሱስ ምን ያደርጋል?

1) ሰዎች ደህንነትን እንዲቀበሉና እንዲያርፉ ይጠራቸዋል፡፡

● ማቴ.11÷28

28. እናንተ ደከሞች ሸክማችሁ የከበደ ሁሉ ወደ እኔ ኑ፣ እኔም ለእናንተ ዕረፍት እሰጣችኋለሁ፡፡

2) የሰይጣንን ሥልጣን ያፈርሳል፡፡

● 1ዮሐ.3÷8 8-ዲያብሎስ ከመጀመሪያው አንሥቶ ኃጢአት ስለሚሠራ ኃጢአትን የሚሠራ ሁሉ የዲያብሎስ ወገን ነው፡፡ የእግዚአብሔር ልጅ የተገለጠውም የዲያብሎስን ሥራ ለማፍረስ ነው፡፡

3) ስለ ክርስቲያኖች ይማልዳል፡፡

● ሮሜ.8÷34 34. ማን ነው የሚፈርድ? ኢየሱስ ክርስቶስ ይፈርድባቸዋልን? እርሱ ስለ እኛ የሞተ፣ ከሞት ተነሥቶ በእግዚአብሔር አብ ቀኝ የተቀመጠ፣ ስለ እኛም የሚማልድ ነው፡፡

4) በኢየሱስ ስም የሚያምኑትን ያድናል፡፡

● ሉቃ.23÷43 43. ኢየሱስም፣ “እኔ እውነት እልሃለሁ፣ ዛሬ ከእኔ ጋር በገነት ትሆናለህ” አለው፡፡

5. በኢየሱስ ስም ላመኑት የሚሰጥ አስር በረከቶች

1) የእግዚአብሔር ልጅ የመሆን በረከት

● ዮሐ.1÷12

12. ነገር ግን ኢየሱስ ራሱ ለተቀበሉትና በስሙ ላመኑት ሁሉ ሰዎች የእግዚአብሔር ልጆች የመሆን መብት ሰጣቸው፡፡

2) የፀሎት ምላሽ የመቀበል በረከት

● ዮሐ.16÷24

24. እስከ አሁን እናንተ በስሜ ምንም ነገር አለመናችሁም፣ ለምኑ ይሰጣችኋል፣ ደስታችሁም ፍጹም ይሆናል፡፡

3) የመንፈስ ቅዱስ አብሮ የመኖር በረከት

● ዮሐ.14÷16-17 16. እኔ አብን እለምናለሁ፣ እርሱም ከእናንተ ጋር ለዘላለም የሚኖር ሌላ አጽናኝ ይሰጣችኋል፣

17. እርሱም የእውነት መንፈስ ነው፣ ዓለም እርሱን ስለማያየውና ስለማያውቀው ሊቀበለው አይችልም፡፡ እናንተ ግን፣ እርሱ ከእናንተ ጋር ስለሚኖርና በውስጣችሁ ስላለ ታውቁታላችሁ፡፡

4) የሰይጣን ሥልጣን የማሸነፍ በረከት

● ሉቃ.10÷19 19-እነሆ! እባብንና ጊንጥን እንድትረግጡ፣ የጠላትንም ኀይል ሁሉ እንድትቋቋሙ ሥልጣን ሰጥቻችኋለሁ፣ የሚጐዳችሁ ምንም ነገር የለም፡፡

5) የጌታ መልአክ ርዳታ የመቀበል በረከት

● ዕብ.1÷14 14-ታዲያ፣ መላእክት ሁሉ የሚድኑትን ሰዎች ለማገልገል የሚላኩ የእግዚአብሔር አገልጋዮች የሆኑ መናፍስት አይደሉምን?

● ኤፌ.6÷1010-በቀረውስ በጌታና በእርሱም ታላቅ ኀይል በርቱ፤

6) የአብርሃም በረከትን የመቀበል በረከት

● ገላ.3÷14 14-ይህም የሆነው እግዚአብሔር ለአብርሃም የሰጠው በረከት በኢየሱስ ክርስቶስ አማካይነት ለአሕዛብ እንዲደርስና እኛም እግዚአብሔር እሰጣችኋለሁ ያለውን መንፈስ ቅዱስን በእምነት እንድንቀበል ነው፡፡

7) የመንግሥተ ሰማይ ዜጎች የመሆን በረከት

● ፊልጵ.3÷20 20-እኛ ግን የሰማይ መንግሥት ዜጎች ነን፤ ከዚያም የሚመጣውን አዳኝ ጌታችንን ኢየሱስ ክርስቶስን በናፍቆት እንጠባበቃለን፡፡

8) የእግዚአብሔር ቤተ መቅደስ የመሆን በረከት

የሲኦል ሥልጣን ቤተክርስቲያንን ልያሸንፍ አይችልም፡፡

● ማቴ.16÷18-19

18. እኔም እንዲህ እልሃለሁ፣ አንተ (ጴጥሮስ)፣ አለት ነህ፣ በዚህችም የመሠረት ድንጋይ ላይ ቤተ ክርስቲያኔን

እሠራለሁ፣ ይህችንም ቤተ ክርስቲያን የሞት ኀይል እንኳ አያሸንፋዋትም፡፡

19. የመንግሥተ ሰማይን መክፈቻዎች እሰጥሃለሁ፣ በምድር ያሰርኸው ሁሉ በሰማይ የታሰረ ይሆናል፣

በምድርም የፈታኸው ሁሉ በሰማይ የተፈታ ይሆናል፡፡”

9) የእግዚአብሔር አምባሳደር (ተወካዮች) የመሆን በረከት

● ዘፍ.1÷28

28-እግዚአብሔርም “ብዙ፣ ተባዙ፣ ዘራችሁም ምድርን ይሙላ፤ ምድርም በቍጥጥራችሁ ሥር ትሁን፤ በባሕር ውስጥ በሚኖሩ ዓሣዎች፣ በሰማይ በሚበርሩ

ወፎችና በምድር ላይ በሚንቀሳቀሱ ሕያዋን ፍጥረቶች ሁሉ ላይ ሥልጣን ይኑራችሁ” ብሎ ባረካቸው፡፡

10) በወንጌል ዓለምን የመውረስ በረከት ናቸው፡፡

● ማቴ.28÷18-20 18-ኢየሱስ ወደ ደቀ መዛሙርቱ ቀረበና እንዲህ አላቸው፤ “ሥልጣን ሁሉ በሰማይና በምድር ተሰጥቶኛል፤19-ስለዚህ እናንተ ወደ ዓለም ሕዝብ ሁሉ ሂዱ፤ በአብ፤ በወልድና በመንፈስ ቅዱስ ስም እያጠመቃችኋቸው የእኔ ደቀ መዛሙርት አድርጉአቸው፡፡

20-እኔ ለእናንተ ያዘዝኋችሁን ሁሉ እንዲጠብቁ አስተምሯቸው፤ እነሆ፤ እኔም እስከ ዓለም መጨረሻ ድረስ ሁልጊዜ ከእናንተ ጋር ነኝ፡፡”

ምዕራፍ ሳባት

7. በወንጌል ምርኮን መማረክ (ዘፍ.1÷26-28)

● ዘፍ.1÷26-28

26-ከዚህ በኋላ እግዚአብሔር “ሰውን በመልካችንና በአምሳያችን እንፍጠር፤ ሰዎችም በባሕር ውስጥ በሚኖሩ ዓሣዎች፣ በሰማይ በሚበርሩ ወፎች፣ በእንስሶችና በምድር ላይ በደረታቸው እየተሳቡ በሚንቀሳቀሱ ፍጥረቶች፣ እንዲሁም በምድር ሁሉ ላይ ሥልጣን ይኑራቸው” አለ፡፡

27-በዚህ ዐይነት እግዚአብሔር ሰውን በራሱ መልክ ፈጠረ፤ በእግዚአብሔር መልክ ፈጠረው፤ ወንድና ሴት አድርጎም ፈጠራቸው፡፡

28-እግዚአብሔርም “ብዙ፣ ተባዙ፣ ዘራችሁ ምድርን ይሙላ፤ ምድርም በቊጥጥራችሁ ሥር ትሁን፤ በባሕር ውስጥ በሚኖሩ ዓሣዎች፣ በሰማይ በሚበርሩ ወፎችና በምድር ላይ በሚንቀሳቀሱ ሕያዋን ፍጥረቶች ሁሉ ላይ ሥልጣን ይኑራችሁ” ብሎ ባረካቸው፡፡

እግዚአብሔር በዚህ ዓለም ላይ ለሰዎች ሰላምና ደስታ ፍፁምም በረከት ሰጥቷቸው ነበር፤ነገር ግን ከሰዎች ኃጢአት የተነሳ እነዚህ በረከቶች ሁሉ ጠፉ፡፡ ይህን የተባረከውን ዓለም ክፉ ወደ ዓለም ሲገባ ፈጽም አበለሸ፡፡ እንዴት ከሰዎች ሰይጣን የወሰደውን በረከት እንደገና መማረክ ይቻላል?

★ እኛ ለራሳችንን የሚንመረመርበት ጥያቄዎች።

① የእግዚአብሔርን ሥራ ዘወትር እሠራለሁ?

② በእኔ በኩል የወንጌል ቃል እየተሰበከ ነው?

③ የእኔ አካባቢ በወንጌል እያደገ ነው?

የክፍት ስብሰባ ለተከታታይ ይሰበካል? በሚሉ ጥያቄዎች ራሳችንን በመጠየቅ ሰይጣን የማረከውን ምርኮ መማረክ ይቻላል፡፡

እግዚአብሔር ለሰዎች የሰጠው በረከት ምንድን ነው?

1) በኤደን ገነት ውስጥ ፍፁም የሚመች አካባቢ አዘጋጅቶ በመስጠት ባረከ፡፡

● ዘፍ.2÷9-15

9-በዚያም ለዐይን የሚያስደስቱና ለምግብነት የሚጠቅሙ ልዩ ልዩ ዛፎች እንዲበቅሉ አደረገ፤ ደግሞም በአትክልቱ ቦታ መካከል ሕይወት የሚሰጥ ዛፍ ነበረ፤ እንዲሁም ደጉን ከክፉ ለመለየት የሚያስችል ዕውቀት የሚሰጥ ሌላ ዛፍ ነበረ፡፡

10-የአትክልት ቦታውን የሚያጠጣ ወንዝ ከዔደን ይፈስ ነበር፤ ይህም ወንዝ ከዔደን ከወጣ በኋላ በአራት ወንዞች ይከፈላል፡፡

11-የመጀመሪያው ወንዝ ፊሶን ይባላል፤ እርሱም ወርቅ በሚገኝበት ሐዊላ በሚባለው ምድር ሁሉ ላይ ይፈስሳል፤

12-የዚያ አገር ወርቅ ንጹሕ ነበር፤ በተጨማሪም በዚያ አገር ውድ የሆነ ሽቶና የከበሩ ድንጋዮች ይገኛሉ፡፡

13-ሁለተኛው ወንዝ ግዮን ይባላል፤ እርሱም ኢትዮጵያ በምትባል አገር ዙሪያ ይፈስሳል፡፡

14-ሦስተኛው ወንዝ ጤግሮስ ይባላል፤ እርሱም በአሶር በስተምሥራቅ ይፈስሳል አራተኛው ወንዝ ኤፍራጥስ ይባላል፡፡

15-ከዚህ በኋላ እግዚአብሔር አምላክ ሰውን በዔደን የአትክልት ቦታ አኖረው፤ ይህንንም ያደረገው ሰው የአትክልቱን ቦታ እንዲያለማና እንዲንከባከበው ነው፡፡

2) እግዚአብሔር የፈጠራቸውን ነገሮች ለመቆጣጠርና ለመጠቀም ሥልጣን በመስጠት ባረከ፡፡

● ዘፍ.1÷27-28

27-በዚህ ዐይነት እግዚአብሔር ሰውን በራሱ መልክ ፈጠረ፤ በእግዚአብሔር መልክ ፈጠረው፤ ወንድና ሴት አድርጎም ፈጠራቸው፡፡

28-እግዚአብሔርም “ብዙ፣ ተባዙ፣ ዘራችሁ ምድርን ይሙላ፤ ምድርም በቊጥጥራችሁ ሥር ትሁን፤ በባሕር ውስጥ በሚኖሩ ዓሣዎች፣ በሰማይ በሚበርሩ ወፎችና በምድር ላይ በሚንቀሳቀሱ ሕያዋን ፍጥረቶች ሁሉ ላይ ሥልጣን ይኑራችሁ” ብሎ ባረካቸው፡፡

3) ከእግዚአብሔር ጋር ኅብረት በመስጠት ባረከ፡፡

● ዘፍ.2÷16-17

16-እግዚአብሔር አምላክ ሰውን እንዲህ ብሎ አዘዘው፡- “በአትክልቱ ቦታ ከሚገኙት ዛፎች ሁሉ ፍሬ ልትበላ ትችላለህ፤

17-ነገር ግን ከእርሱ በበላህበት ቀን በእርግጥ ስለምትሞት ደጉን ከክፉ ለመለየት የሚያስችል ዕውቀት ከሚሰጠው ዛፍ ፍሬ አትብላ፡፡”

4) ጤናማ ሰውነትና የዘላለም ሕይወት በመስጠት ባረከ፡፡

● ዘፍ.1÷28

28-እግዚአብሔርም “ብዙ፣ ተባዙ፣ ዘራችሁ ምድርን ይሙላ፤ ምድርም በቍጥጥራችሁ ሥር ትሁን፤ በባሕር ውስጥ በሚኖሩ ዓሣዎች፣ በሰማይ በሚበርሩ ወፎችና በምድር ላይ በሚንቀሳቀሱ ሕያዋን ፍጥረቶች ሁሉ ላይ ሥልጣን ይኑራችሁ” ብሎ ባረካቸው፡፡

5) ደስተኛ ቤተሰብ በመስጠት ባረከ፡፡

● ዘፍ.2÷24

24-ስለዚህ ወንድ አባቱንና እናቱን ትቶ ከሚስቱ ጋር ይተባበራል፤ ሁለቱም አንድ አካል ይሆናሉ፡፡

ምሳሌ፡- መጽሐፍ ቅዱሳዊ የሆነ ኢኮኖሚና ገንዘብ ለሰው በመስጠት ይባርካል፡፡

ሰይጣን የመጀመሪያ ሰውን አዳምን አስወደቀ፡፡

1) በኃጢአት ምክንያት እኛ ሁሉን አጠጣ።

● ዘፍ.3÷22-24

22-እግዚአብሔር አምላክም እንዲህ አለ፡- “እነሆ፣ አዳም ክፉንና ደጉን በማወቅ ከእኛ እንደ አንዱ ሆነ፤ አሁንም እጁን ዘርግቶ ከሕይወት ዛፍ ወስዶ በመብላት ለዘለዓለም እንዲኖር አይገባም፡፡”

23-በዚህ ምክንያት እግዚአብሔር አምላክ አዳምን ከዔደን የአትክልት ቦታ አስወጣው፤ የተገኘበትንም ምድር እንዲያለማ አደረገው፡፡

24-አዳምንም ካስወጣው በኋላ ከዔደን የአትክልት ቦታ በስተ ምሥራቅ በኩል ኪሩቤል የተባሉትን መላእክትንና በየአቅጣጫው እየተገለባበጠ እንደ እሳት የማንበለበለውን ሰይፍ አኖረ፤ ይህንንም ያደረገው ማንም ወደ ሕይወት ዛፍ እንዳይጠጋ ነው፡፡

2) ሰይጣን ሰውን የዚህ አለም ባሪያ እንዲሆን ያደርጋል፡፡

- 1ዮሐ.2÷15-16

15-ዓለምን ወይም የዓለምን ነገር ሁሉ አትውደዱ፡፡ ዓለምን የሚወድ እግዚአብሔር አብን አይወድም፡፡

16-በዓለም ያለው ሁሉ የሥጋ ምኞት፣ የዐይን አምሮት፣ የኑሮ ትምክሕት ከዓለም ነው እንጂ ከእግዚአብሔር አብ አይደለም፡፡

3) ሰይጣን ታላቅ ሴራ ያደርጋል፡፡ ሰይጣን እኛ ከሰዎች እንድንለይ፣ ሐዘንተኛ እንድንሆን በቁጣ እንዲንሞላ፣

- ራዕ.12÷9

9-ታላቁም ዘንዶ ወደታች ተጣለ፤ እርሱ መላውን ዓለም የሚያስተው ዲያብሎስ ወይም ሰይጣን ተብሎ የሚጠራው የቀድሞው እባብ ነው፡፡ እርሱ ወደ ምድር ተጣለ፤ የእርሱም መላእክት ከእርሱ ጋር አብረው ተጣሉ፡፡

በሐሜትእንዲንሞላ፣በማጉረምረም (መነጫነጭን) እንዲንሞላ ያደርጋል፡፡

- ራዕ.12÷9

9-ታላቁም ዘንዶ ወደታች ተጣለ፤ እርሱ መላውን ዓለም የሚያስተው ዲያብሎስ ወይም ሰይጣን ተብሎ የሚጠራው የቀድሞው እባብ ነው፡፡ እርሱ ወደ ምድር ተጣለ፤ የእርሱም መላእክት ከእርሱ ጋር አብረው ተጣሉ፡፡

4) ሰይጣን ኢየሱስ ክርስቶስን ለመጣል ሞከረ፡፡ ነገር ግን ሰይጣን ራሱ የወደቀ ነው፡፡

● ማቴ.4÷4-11

4. ነገር ግን ኢየሱስም መልሶ። “በመጽሐፍ ቅዱስ እንዲህ ተብሎ ተጽፎአል ‘ሰው በእንጀራ ብቻ አይኖርም ከእግዚአብሔር አፍ በሚወጣ ቃል ሁሉ ይኖራል።’ ”

5. ከዚህ በኋላ ዲያቢሎስ ኢየሱስን ወደ ቅድስት ከተማ ወደ ኢየሩሳሌም ወሰዶ በመቅደስ ጫፍ ላይ አቆመው፣

6. ዲያቢሎስ እንዲህ አለው፡፡ “አንተ የእግዚአብሔር ልጅ ከሆንህ ራስህን ወደ መሬት ወርውር፣ በመጽሐፍት እንዲህ ተብሎ ተጽፎአልና፣ እግዚአብሔር ስለ አንተ ለመላእክቱን ያዝልሃል፣ እነርሱም እግርህ በድንጋይ እንዳይሰናከል በእጃቸው ያነሡሃል፡፡”

7. ኢየሱስም ለዲያቢሎስ መልሶ እንዲህ አለው፡፡ “በመጽሐፍት እንዲህ ተጽፎአል፣ ጌታ እግዚአብሔርህን አትፈታተነው፡፡”

8. እንደገናም ዲያብሎስ ኢየሱስን በጣም ከፍ ወዳለ ተራራ ላይ አውጥቶ፣ የዓለምን መንግሥታት ሁሉ ከነክብራቸው አሳየውና፣

9. ዲያቢሎስ ለኢየሱስ እንዲህ አለው፡፡ “አንተ ለእኔ ወድቀህ ብትሰግድልኝ ይህን ሁሉ እሰጥሃለሁ።”

10. ኢየሱስም መልሶ ለዲያቢሎስ እንዲህ አለው፡፡ “አንተ ሰይጣን ከፊቴ ራቅ! በመጽሐፍት እንዲህ ተጽፎአል፣ ለጌታ ለእግዚአብሔርህ ስገድ፣ እርሱንም ብቻ አምልክ።”

11. ከዚህም በኋላ ዲያቢሎስ ኢየሱስን ትቶት ሄደ፥ መላእክትም መጥተው አገለገሉት፡፡

ሰዎች በሰይጣን ወጥመድ ውስጥ በመግባት የአዕምሮ ህመምተኞች ይሆናሉ፡፡

1) የሥጋ ምኞት እንዲያደርጉ አዕምሮአቸውን ያበላሻል፡፡

● ገላ.5÷17

17-የሥጋ ምኞት ከመንፈስ ምኞት ጋር ይቃረናል፤ መንፈስና ሥጋ እርስ በእርሳቸው ይቃረናሉ፤ ስለዚህ እናንተ የምትፈልጉትን ማድረግ አትችሉም፤

2) በመጨረሻም መዝሙር ኃጢአት እንዲወድቁ ያደርጋል፡፡

● ገላ.5÷19

19-የሥጋ ሥራዎች የታወቁ ናቸው፤ እነርሱም ዝሙት፣ ርኩሰት፣ ስድነት … ወዘተ ናቸው።

3) የጣኦት አምልኮ ሲያደርጉ ለይተው የሚያቁበት ዓይን የላቸውም፡፡

● ገላ.5÷20

20-ጣዖትን ማምለክ፣ ሟርት፣ ጠላትነት፣ ንትርክ፣ ቅናት፣ ቊጣ፣ ራስ ወዳድነት፣ መለያየተ፣ አድመኛነት፣

4) በራስ ወዳድነት ምኞት ይወድቃሉ፡፡

● ገላ.5÷21

21-ምቀኝነት፣ ስካር፣ ቅጥ ያጣ ፈንጠዝያ እነዚህን የመሳሰሉ ናቸው፤ ከዚህ በፊት እንዳስጠነቀቅኋችሁ አሁንም ደግሞ አስጠነቅቃችኋለሁ፤ እንደ እነዚህ ያሉትን ነገሮች የሚያደርጉ ሰዎች የእግዚአብሔርን መንግሥት አይወርሱም፡፡

5) ከንቱ ውዳሴ (ክብር) በመከተል ዓመትን እንዲባክኑ ያደርጋል፡፡

● ገላ.5÷26

26-አንዱ ሌላውን ለክፋ በማነሣሣት እርስ በእርሳችን እየተቀናናን በከንቱ አንመካ፤

ከዚህ ከተበላሸው ስቃይ ቦታ ማውጣት የሚችለው ኢየሱስ ብቻ ነው፡፡

1) ኢየሱስ የመጣበት ምክንያትና ግብ

● ገላ.3÷13-14

13-“በእንጨት ላይ ተሰቅሎ የሚሞት ሁሉ የተረገመ ነው” ተብሎ ስለ ተጻፈ ክርስቶስ ስለ እኛ እንደ ተረገመ ሰው ሆኖ ሕግ ከሚያስከትለው ርግማን ዋጀን፡፡

14-ይህም የሆነው እግዚአብሔር ለአብርሃም የሰጠው በረከት በኢየሱስ ክርስቶስ አማካይነት ለአሕዛብ እንዲደርስና እኛም እግዚአብሔር እሰጣችኋለሁ ያለውን መንፈስ ቅዱስን በእምነት እንድንቀበል ነው፡፡

የእኛን ርግማን ለመደምሰስ

የአብርሃም በረከት ለመስጠት

መንፈስ ቅዱስን በእኛ(በእኔ) መካከል ለማኖር

2) በዚህ በረከት ለመኖር መንገዱ ምንድን ነው? ኢየሱስ ክርስቶስን ስናምን በዚህ በረከት መኖር ይቻላል፡፡

● ዮሐ.1÷12

12. ነገር ግን ኢየሱስ ራሱ ለተቀበሉትና በስሙ ላመኑት ሁሉ ሰዎች የእግዚአብሔር ልጆች የመሆን መብት ሰጣቸው፡፡

3) ከዚያ በኋላ መንፈስ ቅዱስ አብሮ ይኖራል፡፡

● ሮሜ. 8÷14

14-በእግዚአብሔር መንፈስ የሚመሩ ሁሉ የእግዚአብሔር ልጆች ናቸው፡፡

በወንጌል ሰይጣን የማረከውን በረከት እንደገና መማረክ

1) ወንጌል ማለት የሰውን ችግሮች ሁሉ የሚፈታና የኢየሱስ ክርስቶስ የመስቀል ድል ማለት ነው፡፡

● ቆላ.2÷13-15

13-ኃጢአት በመሥራታችሁና ይህ ኃጢአተኛ ሥጋችሁ በክርስቶስ በማመን ባለመገረዙ ምክንያት ሙታን ነበራችሁ፤ አሁን ግን እግዚአብሔር ከክርስቶስ ጋር ሕያዋን አድርጓችኋል፤ ኃጢአታችሁንም ሁሉ ይቅር ብሎላችኋል፡፡

14-እርሱ ያንን ይከሰንና ይቃወመን የነበረውን በሕግ ያለውን የዕዳ ጽሑፍ ደመሰሰው፤ በመስቀል ላይ ቸንክሮም ከእኛ አስወገደው፡፡

15-ኀይላትንና ባለሥልጣናትን በመስቀሉ ድል ነሥቶ ትጥቃቸውን ካስፈታ በኋላ ምርኮኞች ሆነው በይፋ እንዲታዩ አደረጋቸው፡፡

2) በአዳም ምክንያት የጠፋውን በረከቶች በኢየሱስ በኩል እንደገና በመማረክ የአብርሃምን በረከቶች መቀበል ነው፡፡

● ገላ.3÷13-14

13-“በእንጨት ላይ ተሰቅሎ የሚሞት ሁሉ የተረገመ ነው” ተብሎ ስለ ተጻፈ ክርስቶስ ስለ እኛ እንደ ተረገመ ሰው ሆኖ ሕግ ከሚያስከትለው ርግማን ዋጀን፡፡

14-ይህም የሆነው እግዚአብሔር ለአብርሃም የሰጠው በረከት በኢየሱስ ክርስቶስ አማካይነት ለአሕዛብ እንዲደርስና እኛም እግዚአብሔር እሰጣችኋለሁ ያለውን መንፈስ ቅዱስን በእምነት እንድንቀበል ነው፡፡

3) በተትረፈረፈ ሕይወት መኖር

● ዮሐ.10÷10

10. ሌባው ሊሰርቅ፣ ሊገድልና ሊያጠፋ ብቻ ይመጣል፣ እኔ የመጣሁት በጎቼ ሕይወት እንዲያገኙና የተትረፈረፈ ሕይወት እንዲኖራቸው ነው፡፡

4) በኢየሱስ ስም ወንጌልን መኖር፡፡

● ሐዋ.16÷31

31-ጳውሎስና ሲላስም፣ “በጌታ በኢየሱስ እመን፤ አንተም ቤተ ሰዎችህም ትድናላችሁ” አሉት፡፡

5) በወንጌል ለሚኖር ሰው በረከቶች ሁሉ ተሰጥቶታል፡፡

● ማቴ.28÷18

18-ኢየሱስ ወደ ደቀ መዛሙርቱ ቀረበና እንዲህ አላቸው፣ “ሥልጣን ሁሉ በሰማይና በምድር ተሰጥቶኛል፣

ምዕራፍ ስምንት

8. በፀሎት ልዩ ሥልጣን መኖር (ዮሐ.16÷24)

● ዮሐ.16÷24

24. እስከ አሁን እናንተ በስሜ ምንም ነገር አለመናችሁም፤ ለምኑ ይሰጣችኋል፤ ደስታችሁም ፍጹም ይሆናል፡፡

ኢየሱስን ያመኑ ሰዎች የእግዚአብሔር ልጆች የመሆንን ሥልጣን ይቀበላሉ፡፡ ክርስቲያኖች ወደ እግዚአብሔር በመፀለይ ማንኛውንም የሚፈልጉትን ነገር የማግኘት ልዩ ሥልጣን አላቸው፡፡ በዚህ ምድር ብዙ ሃይማኖቶች ፀሎት ያደርጋሉ፡፡ ነገር ግን ፀሎትን ከፀለዩ በኋላ መልስ አያገኙም፡፡ ወደ እግዚአብሔር ብቻ የሚፀልይ ሰው ጸሎት አይወድቅም፡፡ ምክንያቱም እግዚአብሔር መልስ የመስጠት ተስፋ ስላለው ነው፡፡ እግዚአብሔር አሁን የሚፀልይ ሰውን የዳኑ ይፈልጋል፡፡

★ በኢየሱስ ያመኑ ሰዎች ለውጥ ምንድን ነው?

① ሁሉ ከእርግማን ነጻ መሆን።

② ከሰይጣን እስረት መወጣት።

③ በኢየሱስ ስም ላመኑት የሚሰጥ 10 በረከቶች መቀበል:: (ምዕራፍ አምስትን - 5- ተመልከት)

ውጤት - ኢየሱስን በትክክል ያመኑ ሰዎች ታላቅ በረከቶች ይቀበላሉ:: በየቀኑ በኢየሱስ ውስጥ መኖር።

1. ፀሎት ማለት ምን ማለት ነው?

1) የእግዚአብሔር ልጅ የሰጠው ልዩ ስልጣን ነው፡፡

● ዮሐ.1÷12

12. ነገር ግን ኢየሱስ ራሱ ለተቀበሉትና በስሙ ላመኑት ሰዎች ሁሉ የእግዚአብሔር ልጆች የመሆንን መብት ሰጣቸው፡፡

2) ከእግዚአብሔር ጋር መነጋገር (ህብረት ማድረግ) ማለት ነው፡፡

● መዝ.16÷8-9

8-ሁልጊዜ እግዚአብሔርን በፊቴ አየዋለሁ በቀኜ ነውና አልታወክም።

9-ስለዚህ ልቤን ደስ አለው ምላሴም ሐሴት አደረገች ሥጋዬም ደግሞ በተስፋ ታድራለች

3) ከእግዚአብሔር የምንፈልገውን በፀሎት መቀበል ማለት ነው፡፡

● ማቴ.6÷6-9

6. ነገር ግን አንተ ስትጸልይ፥ ወደ ክፍልህ ገብተህ፣ በርህን ዝጋና በስውር ወዳለው ወደማይታይ አባትህ ጸልይ፣ በስውር የተደረገውን የሚያይ አባትህም ለአንተ የመልካም ሥራህን ዋጋ ይከፍልሃል።

7. እናንተ ስትጸልዩ እንደ አሕዛብ ከንቱ ቃል አትድገሙ። እነርሱ ብዙ ቃላት በመናገራቸው እግዚአብሔር እንደሚሰማላቸው ያስባሉ፡፡

8. እናንተ እንደ አሕዛብ አትጸልዩ፤ አባታችሁ ከመለመናችሁ በፊት ለእናንተ ምን እንደሚያስፈልጋችሁ ያውቃልና።

9. ስለዚህ እናንተ እንዲህ ብላችሁ ጸልዩ፣ “በሰማይ የምትኖር አባታችን ሆይ፣ ስምህ ይቀደስ፣

4) በኢየሱስ ስም የምንፈልገውን ማግኘት

● ዮሐ.16÷23-24

23. በዚያ ቀን ከእኔ ምንም አትለምኑም፣ እውነት፣ እውነት እላችኋለሁ እናንተ አብን በስሜ የምትለምኑትን ሁሉ ይሰጣችኋል፡፡

24. እስከ አሁን እናንተ በስሜ ምንም ነገር አለመናችሁም፣ ለምኑ ይሰጣችኋል፣ ደስታችሁም ፍጹም ይሆናል፡፡

5) የመንፈስ ቅዱስ ርዳታ ማግኘት ማለት ነው፡፡

● ሮሜ.8÷26-27

26. እንዲሁም ደግሞ መንፈስ በድካማችን ያግዘሃል፤ እንዴት ማጸለይ እንደሚገባን አናውቅም፤ መንፈስ ግን በቃላት ሊገለጥ በማይችል መቃተት ለእኛ ይማልድልናል፡፡

27. ልባችንንም የሚመረምረው እርሱ የመንፈስን ሐሳብ ያውቃል፤ ምክንያቱም መንፈስ እንደ እግዚአብሔር ፈቃድ ለቅዱሳን ይማልዳልና፡፡

2. እግዚአብሔር እኛን በጣም ይወድዳናል፡፡

1) እኛን በእውነት የሚወድድ እግዚአብሔር ነው፡፡

● ዮሐ.3÷16

16. እግዚአብሔር ዓለምን እጅግ ስለ ወደደ አንድያ ልጁን ሰጠ፣ ይህም በኢየሱስ የሚያምን ሁሉ እንዳድንነው እንጂ እንዳይጠፋ የዘላለም ሕይወት እንዲኖረው አደረገ፡፡

2) እግዚአብሔር ለእኛ የተትረፈረፈ ሕይወት ሰጠ፡፡

● ዮሐ.10÷10

10. ሌባው ሊሰርቅ፣ ሊገድልና ሊያጠፋ ብቻ ይመጣል፣ እኔ የመጣሁት በጎቼ ሕይወት እንዲያገኙና የተትረፈረፈ ሕይወት እንዲኖራቸው ነው፡፡

3) እግዚአብሔር እውነተኛ ረዳት ነው፡፡

● ዕብ.13÷6

6-ስለዚህ በመተማመን፣ "ጌታ ረዳቴ ነው፤ አልፈራም፤ ሰው ምን ሊያደርገኝ ይችላል?" እንላለን፡፡

4) እኛን ሁል ጊዜ ይባርካል፡፡

● ዘዳ.28÷1-14

1-እንዲህም ይሆናል የአምላክህን የእግዚአብሔርን ቃል ብትሰማ፥ ዛሬም ያዘዝሁህን ትእዛዙን ሁሉ ብታደርግ ብትጠብቅም አምላክህ እግዚአብሔር ከምድር አሕዛብ ሁሉ ላይ ከፍ ከፍ ያደርግሃል።

2-የአምላክህንም የእግዚአብሔርን ቃል ብትሰማ እነዚህ በረከቶች ሁሉ ይመጡልሃል ያገኙህማል።

3-አንተ በከተማ ቡሩክ ትሆናለህ፥ በእርሻም ቡሩክ ትሆናለህ።

4-የሆድህ ፍሬ፥ የምድርህም ፍሬ፥ የከብትህም ፍሬ፥ የላምህም ርቢ፥ የበግህም ርቢ ቡሩክ ይሆናል።

5-እንቅብህና ቡሃቃህ ቡሩክ ይሆናል።

6-አንተም በመግባትህ ቡሩክ ትሆናለህ፥ በመውጣትህም ቡሩክ ትሆናለህ።

7-እግዚአብሔርም በላይህ የሚቆሙትን ጠላቶችህን በፊትህ የተመቱ ያደርጋቸዋል በአንድ መንገድ ይመጡብሃል፥ በሰባትም መንገድ ከፊትህ ይሸሻሉ።

8-እግዚአብሔር በረከቱ በአንተ ላይ በጐተራህ በእጅህም ሥራ ሁሉ እንዲወርድ ያዝዛል አምላክህ እግዚአብሔር በሚሰጥህም ምድር ይባርክሃል።

9-የአምላክህን የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ብትጠብቅ፥ በመንገዱም ብትሄድ፥ እግዚአብሔር እንደ ማለልህ ለእርሱ የተቀደሰ ሕዝብ አድርጎ ያቆምሃል።

10-የምድር አሕዛብም ሁሉ የእግዚአብሔር ስም በአንተ ላይ እንደ ተጠራ አይተው ይፈሩሃል።

11-እግዚአብሔርም እርስዋን ይሰጥህ ዘንድ ለአባቶችህ በማለላቸው በምድርህ ላይ፥ በሆድህ ፍሬ፥ በከብትህ ፍሬ፥ በእርሻህም ፍሬ፥ እግዚአብሔር በጎነቱን በላይህ ያበዛል።

12-እግዚአብሔርም ለምድርህ በወራቱ ዝናብ ይሰጥ ዘንድ፥ የእጅህንም ሥራ ሁሉ ይባርክ ዘንድ መልካሙን መዝገብ ሰማዩን ይከፍትልሃል ለብዙ አሕዝብም ታበድራለህ፥ አንተ ግን ከማንም አትበደርም።

13-14-ዛሬም ያዘዝሁህን የአምላክህን የእግዚአብሔርን ትእዛዝ ሰምተህ ብትጠብቃት ብታደርጋትም፥ ዛሬም ካዘዝሁህ ከእነዚህ ቃሎች ወደ ቀኝ ወደ ግራም ፈቀቅ ባትል፥ ታመልካቸውም ዘንድ ሌሎችን አማልክት ባትከተል፥ እግዚአብሔር ራስ ያደርግሃል እንጂ ጅራት አያደርግህም ሁልጊዜም በላይ እንጂ በታች አትሆንም።

5) በመንፈስንና በሥጋ እንዲናድግ የእግዚአብሔር ፈቃድ ነው፡፡

እኛ ወደ እግዚአብሔር ስንፀልይ ለምን ይመልሳል? ስለሚወደን ነው፡፡

- 3ዮሐ.1÷2

2-ወዳጄ ሆይ! ኑሮህ ሁሉ እንዲሳካልህ፣ ጤንነት እንዲኖርህና እንዲሁም የመንፈስ እርካታ እንድታገኝ እመኝልሃለሁ፡፡

3. ፀሎት በእግዚአብሔር ፍቅር የምንመካበት ነው፡ ፡

1) በማንኛውም ነገር እንድንጨነቅ አያስፈልግም፡ ፡ ሁል ጊዜ በማመስገን መፀለይ ያስፈልጋል፡ ፡

● ፊልጵ.4÷6

6-ጌታ ቅርብ ነው። በነገር ሁሉ በጸሎትና በምልጃ ከምስጋና ጋር በእግዚአብሔር ዘንድ ልመናችሁን አስታውቁ እንጂ በአንዳች አትጨነቁ።

2) ስንፀልይ ደስተኞች መሆን አለብን፡ ፡

● ዮሐ.16÷24

24. እስከ አሁን እናንተ በስሜ ምንም ነገር አለመናችሁም፣ ለምኑ ይሰጣችኋል፣ ደስታችሁም ፍጹም ይሆናል፡ ፡

3) ሳናቋርጥ መፀለይ አለብን፡ ፡

● 1ተሰ.5÷17-18

18-ሳታቋርጡ ጸልዩ፤ በሁሉ አመስግኑ፤ ይህ የእግዚአብሔር ፈቃድ በክርስቶስ ኢየሱስ ወደ እናንተ ነውና።

4) የእግዚአብሔርን ቃል በማመን መፀለይ አለብን፡ ፡

● 1ጴጥ.2÷2

2-አዲስ የተወለዱ ሕፃናት ወተት እንደሚመኙ እናንተም ለመዳን እያደረጋችሁ የምትሄዱበትን ንጹሑን መንፈሳዊ ትምህርት ተመኙ፡ ፡

5) በመንፈስ ቅዱስ ውስጥ ሆነን ሁል ጊዜ መፀለይ አለብን፡ ፡

● ኤፌ.6÷18

18-ዘወትር በመንፈስ ቅዱስ እየተመራችሁ ጸሎትንና ልመናን አቅርቡ፡ ፡

★ ሰይጣን እኛ የእግዚአብሔርን ፍቅር እንድንጠራጠር ያደርጋል፡፡

① እግዚአብሔር ሁልጊዜ እኛን ይወድዳል፡፡

● 1ጴጥ.5÷8-9

8-በመጠን ኑሩ፤ ንቁም! ጠላታችሁ ዲያብሎስ የሚውጠውን በመፈለግ እንደሚያገሣ አንበሳ በዙሪያችሁ ይንጐራደዳል፡፡

9-በዓለም ሁሉ ያሉ ወንድሞቻችሁ ይህን ዐይነት መከራ እንደሚቀበሉ በማወቅ በእምነት ጸንታችሁ ተቃወሙት፡፡

② ሰይጣን በብዙ መንገድ እኛን ለመጣል ይፈልጋል፡፡

● ኤፌ.6÷10-13

10-በቀረውስ በጌታና በእርሱም ታላቅ ኀይል በርቱ፤

11-የዲያብሎስን የተንኰል ሥራ ለመቃወም እንድትችሉ የእግዚአብሔርን የጦር መሣሪያ በሙሉ ልበሱ፡፡

12-የእኛ ውጊያ ከሰዎች ጋር ሳይሆን በዚህ በጨለማ ዘመን ከሚሠሩት ገዢዎች፣ ሥልጣናት ከዚህ ዓለም ኀይላት ነው። ይህም ማለት በሰማይ ካሉት ከርኩሳን መናፍስት ሠራዊት ጋር ነው፡፡

13-ስለዚህ በክፉ ቀን የጠላትን ኀይል ለመቋቋም እንድትችሉና ሁሉንም ፈጽማችሁ ጸንታችሁ ለመቆም እንድትችሉ የእግዚአብሔርን ሙሉ የጦር መሣሪያ አንሡ!

③ ሰይጣን የእግዚአብሔርን ቃል ተጠራጥረን ኃጢአት እንድናደርግ ያደርጋል፡፡

● ያዕ.4÷2

2-አንድን ነገር ለማግኘት ትመኛላችሁ፤ ግን አታገኙም፤ ስለዚህ ሰውን ትገድላላችሁ፡፡ ስለማትጸልዩም የምትፈልጉትን ነገር አታገኙም፡፡

④ ሰይጣን ከእግዚአብሔር ፍቅር ተለይተን ጣኦትን እንድናመልክ ያደርጋል፡፡

● 1ቆሮ.10÷21

21-የጌታን ጽዋ እየጠጣችሁ ደግሞ የአጋንንትን ጽዋ መጠጣት አትችሉም፤ የጌታ ማእድ ተካፋዮች ሆናችሁ ደግሞ የአጋንንትን ማእድ ተካፋይ መሆን አትችሉም፤

4. የፀሎት መልስ በቅደም ተከተል ይመጣል?

1) በመንፈስ ቅዱስ የትጐደውን ስሜት በማደስ ይመጣል፡፡

● ፊልጵ.4÷6-7

6-ጌታ ቅርብ ነው። በነገር ሁሉ በጸሎትና በምልጃ ከምስጋና ጋር በእግዚአብሔር ዘንድ ልመናችሁን አስታውቁ እንጂ በአንዳች አትጨነቁ።

7-አእምሮንም ሁሉ የሚያልፍ የእግዚአብሔር ሰላም ልባችሁንና አሳባችሁን በክርስቶስ ኢየሱስ ይጠብቃል።

2) የሚረዳንን ሰው በመግለጥ ይመጣል፡፡

● ሐዋ.16÷14

14-ይሰሙን ከነበሩትም ሴቶች መካከል ልድያ የምትባል አንዲት ሴት ነበረች፤ ልድያ እግዚብሔርን የምታመልክና ከተያጥሮን ከተማ የመጣች የቀይ ሐር ነጋዴ ነበረች፤ ጳውሎስም የሚናገረውን ታዳምጥ ዘንድ ጌታ ልብዋን ከፈተላት።

3) ፀሎት የፀሎትን ምላሽ በትዕግስት እንድንጠብቅ ያደርጋል፡፡

● ያዕ.1÷6

6-ነገር ግን ሰው ምንም ሳይጠራጠር በእምነት ይለምን፤ የሚጠራጠር ሰው በነፋስ የተገፋና የተናወጠ የባሕር ማዕበል ይመስላል፡፡

4) የመላዕክትን ርዳታ በማብዛት ይመጣል፡፡

● ራዕ.8÷3-4

3-የወርቅ ጥና የያዘ ሌላ መልአክ መጣና በመሠዊያው አጠገብ ቆመ፤ በዙፋኑ ፊት ባለው የወርቅ መሠዊያ ላይ ከቅዱሳን ጸሎት ጋር የሚያቀርበው ብዙ ዕጣን ተሰጠው፡፡

4-የዕጣኑ ጢስ ከቅዱሳን ጸሎት ጋር ከመልአኩ እጅ ወደ እግዚብሔር ፊት ወጣ፡፡

5) የምንፈልገውን ከላይ ታላቅ መልስ በመስጠት ይመጣል፡፡

● ያዕ.1÷5

5-ከእናንተ መካከል ጥበብ የጐደለው ሰው ቢኖር እግዚአብሔርን ይለምን፤ እግዚአብሔርም ይሰጠዋል፤ እርሱ ምንም ቅር ሳይለው ለሁሉም በልግሥና የሚሰጥ ቸር

አምላክ ነው፡ ፡

6) በፀሎት በኩል የተትረፈረፈ ሕይወትና አስተማማኝ እምነት እንዲኖር ያደርጋል፡ ፡

● ፊልጵ.4÷6-8

6-ጌታ ቅርብ ነው። በነገር ሁሉ በጸሎትና በምልጃ ከምስጋና ጋር በእግዚአብሔር ዘንድ ልመናችሁን አስታውቁ እንጂ በአንዳች አትጨነቁ።

7-አእምሮንም ሁሉ የሚያልፍ የእግዚአብሔር ሰላም ልባችሁንና አሳባችሁን በክርስቶስ ኢየሱስ ይጠብቃል።

8-በቀረውስ፥ ወንድሞች ሆይ፥ እውነተኛ የሆነውን ነገር ሁሉ፥ ጭምትነት ያለበትን ነገር ሁሉ፥ ጽድቅ የሆነውን ነገር ሁሉ፥ ንጹሕ የሆነውን ነገር ሁሉ፥ ፍቅር ያለበትን ነገር ሁሉ፥ መልካም ወሬ ያለበትን ነገር ሁሉ፥ በጎነት ቢሆን ምስጋናም ቢሆን፥ እነዚህን አስቡ፤

5. የፀሎትን መልስ የመቀበል ሚስጢር

1) ከእግዚአብሔር ጋር በሰላም ስንኖር፡ ፡

● ኢዮ.22÷21

21-አሁንም ከእርሱ ጋር ተስማማ፥ ሰላምም ይኑርህ

በዚያም በጎነት ታገኛለህ።

2) በኢየሱስ ስም አምነን የእግዚአብሔር ልጅ ስንሆን

● ዮሐ.1÷12

12. ነገር ግን ኢየሱስ ራሱ ለተቀበሉትና በስሙ ላመኑት ሁሉ ሰዎች የእግዚአብሔር ልጆች የመሆን መብት ሰጣቸው፡ ፡

3) በመንፈስ ቅዱስ ተመርኩዘን ስንፀልይ

● 1ዮሐ.5÷14

14-ማንኛውንም ነገር እንደ እርሱ ፈቃድ ብንለምን እንደሚሰማን እንተማመናለን፡ ፡

4) መልስ እስከሚመጣ ድረስ በመታገስ በአስተማማኝ እምነት ስንፀልይ

● ዕብ.11÷6

6-ያለእምነት እግዚአብሔርን ደስ ማሰኘት አይቻልም፤ ወደ እግዚአብሔር የሚቀርብ ሰው እግዚአብሔር መኖሩንና እርሱን ለሚፈልጉት ሰዎችም ስጦታን የሚሰጥ መሆኑን ማመን አለበት፡፡

5) ያለ ጥርጥር ስንፀልይ

- ያዕ.1÷6

6-ነገር ግን ሰው ምንም ሳይጠራጠር በእምነት ይለምን፤ የሚጠራጠር ሰው በነፋስ የተገፋና የተናወጠ የባሕር ማዕበል ይመስላል፡፡

ምዕራፍ ዘጠኝ

9. ከህመምና ከስቃይ ነፃ መውጣት (ማር.16÷17-18)

● ማር.16÷17-18

17. የሚያምኑትን እነዚህ ምልክቶች ይከተሉአቸዋል፣ በስሜ አጋንንትን ያወጣሉ፣ በአዲስ ልሳንም ይናገራሉ፣

18. እባቦች ቢይዙ፣ ወይም የሚገድል መርዝ እንኳ ቢጠጡ አይጐዳቸውም፣ እጃቸውን በበሽተኞች ላይ ሲጭኑ እነርሱም ይድናሉ፡፡"

ኢየሱስ ክርስቶስ ወንጌልን በሚሰብክበት ጊዜ የራሱ 67% ሕይወት ህመምተኞችን ይፈወስ ነው፡፡ ብዙ ሰዎች በብዙ ህመም የሚሰቃዩት አሉ፡፡ እግዚአብሔር የሰዎችን ስቃይ አይቶ አዘነላቸው፡፡ እግዚአብሔር ሰዎችን ከህመማቸው ነፃ ለማውጣት ይፈልጋል፡፡ ኢየሱስ ክርስቶስ ትላንትና፤ ዛሬ ለዘላለምም ያው ነው፡፡ አሁን ባመኑት ሰዎች በኩል እየሠራ ለቤተክርስቲያን ፈውስን ያመጣል፡፡ ይህ ሥራ አሁን ይገለጣል፡፡

★ የፈውስ አገልግሎት ከመደረጉ በፊት የሚደረጉ ጥንቃቄዎች፡፡

① ህመምተኞችን ከመፈወስ በፊት ኢየሱስን እንዲቀበሉ ያስፈልጋል፡፡

② በንስሐ በኩል የልብና የሥጋ ፈውስ እንድሆን ያስፈልጋል፡፡

ክታብንና የጣኦት አስቀድሞ ማውጣት ያስፈልጋል፡፡

ማምለክያና ጠንቋይ የሰጣቸው መዲሃኒቶች በቤታቸው ካለ ማውጣት ያስፈልጋል፡፡

★ በመንፈስ ህመም የተያዙ ሰዎች ምን ቅርጽአላቸው?

① ፀሎት አይፀልዩም፡፡ ብዙ ሀሳብ አላቸው ነግር ግን እንቅልፋሞች ናቸው፡፡

② በአምልኮ ጊዜ ስብከት አይሰሙም፡፡

③ በእግዚአብሔር ቃል አይመሩም፡፡

ምሳሌ፡- የዓለም ታሪክ ይናገራሉ፡፡ ተረትን ይወዳሉ ነግር ግን የወንጌልን ሥራ አይወዱም፡፡

④ከቤተክርስቲያን ጋር ግንኙነት የላቸውም፤

ውጤት፡- እነዚህን ሰዎች ወንጌላዊ (አገልጋዩ) በሥልጣንና በጌታ ፍቅር ነፃ ያወጣሉ፡፡

1. አስቀድሞ የህመም ምንጭ መመርመር አለበት

1) የሥጋ ህመም

ብዙ ሥራ ስለሠራ ድካም፤ ባክቴሪያ፤ የተለያዩ በሽታዎች፣የሽምግልና መጫጫን ከአያቶቻቸው የውርስ በሽታ ወዘተ.. መኖራቸውን መመርመር

● ዘፍ.48÷1

1-ጥቂት ጊዜ ካለፈ በኋላ “አባትህ ታሞአል” ተብሎ ለዮሰፍ ተነገረው፤ ስለዚህ ዮሴፍ ሁለቱን ልጆቹን ምናሴንና ኤፍሬምን ይዞ ያዕቆብን ለማየት ሄደ፡፡

● ዘፍ.48÷10

10-የያዕቆብ ዐይኖች በእርጅናው ምክንያት ስለ ደከሙ አጥርቶ ማየት አይችልም ነበር፤ ስለዚህ ዮሴፍ ልጆቹን ወደ እርሱ አቀረበለት፤ እርሱም ዕቅፍ አድርጎ ሳማቸው፡፡

2) የበደል ህመም

የጥፋትና የድንገተኛ አደጋ መድረስ፤ በስካር ምክንያት መታመም

● ሆሴዕ.7÷5

5-በንጉሣችን ቀን አለቆች ከወይን ጠጅ ሙቀት የተነሣ ታመሙ፤ እርሱም ከዋዘኞች ጋር እጁን ዘረጋ።

3) የእግዚአብሔር ፈቃድ የሆነ ህመም

● ዮሐ.9÷1-3

1. ኢየሱስ በመንገድ ሲያልፍ ከተወለደ ጀምሮ ዕውር የሆነውን ሰው አየ።

2. ደቀ መዛሙርቱም ኢየሱስን እንዲህ ሲሉ ጠየቁት፣ ይህ ሰው ዕውር ሆኖ እንዲወለድ የማን ኃጢአት ምክንያት ነው? እርሱ ራሱ ወይስ ወላጆቹ?”

3. ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰ፣ “ይህ ሰው ዕውር ሆኖ እንዲወለድ በእርሱ ወይም በወላጆቹ ኃጢአት ምክንያት አይደለም፣ ነገር ግን ይህ የሆነው የእግዚአብሔር ሥራ በእርሱ እንዲገለጥ ነው፡፡

- የዓይነ ስውሩን ዓይን ኢየሱስ ፈወሰው፡፡

- ለሐዋሪያ ጳውሎስ በትንሹ የማየት በሽታ ከእግዚ/ር ዘንድ የተሰጠ “የሥጋዬ መውጊያ” ብሎ የተናገረው ቃል ነው፡፡

● 2ቆሮ 12÷7

7-ከነዚህ ከተገለጡልኝ ታላላቅ ነገሮች የተነሣ እንዳልታበይ ሥጋዬን እንደ እሾኽ የሚወጋ ሥቃይ ተሰጠኝ፤ ይህም የሰይጣን መልእክተኛ በመሆን እየጐሸመ በማሠቃየት እንዳልታበይ ያደርገኛል፡፡

4) በኃጢአት ምክንያት የሚመጣ ህመም

① በአዳም ኃጢአት ምክንያት የሚመጣ ህመም

የአዳም ኃጢአት ርግማኔ ነው፡፡ ነገር ግን ኢየሱስ ያመኑትን ሰዎች ከርግማኔ ነፃ አውጥቶ መፍትሄን ይሰጣል፡፡

● ዘፍ.3÷16-19

16-ሴቲቱንም፣ “በእርግዝናሽ ወራት ጭንቀትሽን፣ በምትወልጂበትም ጊዜ የምጥ ሥቃይሽን አበዛሁ፤ ይህም ሁሉ ሆኖ ፍላጎትሽ ለባልሽ ይሆናል፡፡ ለእርሱም ታዛዥ ትሆኚአለሽ” አላት፡፡

17-አዳምንም እንዲህ አለው፣ “የሚስትህን ቃል ሰምተህ ‘አትብላ’ ያልኩህን ፍሬ ከዛፉ ወስደህ ስለ በላህ፣ አንተ በፈጸምከው ክፉ ሥራ ምክንያት ምድር የተረገመች ትሁን፤ በሕይወት ዘመንህ ሁሉ ምግብህን ከእርስዋ የምትበላው በብርቱ ድካም ነው፡፡

18-ምድር እሾኽና አሜከላ ታበቅላለች፤ አንተም የዱር ተክሎችን ትበላለህ፡፡

19-ወደ መጣህበት ወደ መሬት እስክትመለስ ድረስ፣ እንጀራህን በግንባርህ ላብ ትበላለህ፡፡” ዐፈር ነህና፣ ወደ ዐፈርም ትመለሳለህ፡፡

② በሕይወት በሚኖሩበት ዘመን የሠሩት ኃጢአት

● 1ቆሮ.5÷5

5-በኃጢአት የተሞላው የዚህ ሰው ሥጋ ይፈርስ ዘንድ ለሰይጣን አሳልፋችሁ ልትሰጡት ይገባል፡፡ ይህንንም የምታደርጉት ጌታ ኢየሱስ ለፍርድ በሚመጣበት ቀን የዚህ ሰው ነፍስ እንድትድን ነው፡፡

③ ከአያቶች ኃጢአት ምክንያት የሚመጣ ህመም

● ዘፀ.20÷4-5

4-በሰማይም ሆነ በምድር ወይም ከምድር በታች ባለው ውሃ ውስጥ ከሚኖሩት ነገሮች የማንኛውንም ዐይነት ምስል ጣዖት አድርገህ አትሥራ፤

5-እኔ እግዚአብሔር አምላክህ እጅግ ቀናተኛ ስለ ሆንኩ ተቀርጾ የተሠራውን ማንኛውም ጣዖት አታምለክ፤ አትስገድለትም፤ እኔ የሚጠሉኝን ሁሉ እቀጣለሁ፤ ዘራቸውንም ሁሉ እስከ ሦስትና አራት ትውልድ ድረስ እበቀላለሁ፡፡

④ ከሰይጣን የሚመጣ ህመም፤ የአዕምሮ ህመም የልብ ጉዳት ህመም የስጋ ህመም (የማየት ችግር፣የመስማት ችግር) የአካባቢ ጉዳት መመርመር ያስፈልጋል፡፡

2. ህመምተኞች እንደሚፈወሱ የተስፋ ቃል በመጽሐፍ ቅዱስ ውስጥ አለ፡፡

1) እኔንና እናንተን የሚፈውስ እግዚአብሔር ነው፡፡ [2]… ፈዋሻችሁ እኔ እግዚአብሔር ነኝና[2]

● ዘፀ.15÷26

26-እንዲህም አላቸው፤ “በጥሞና ትእዛዞቼን ብታዳምጡና በፊቴ መልካም የሆነውን ነገር በታዛዥነት ብታደርጉ፣ ሕጎቼንም ሁሉ ብትጠበቁ፣ በግብጻውያን ላይ ካመጣሁባቸው በሽታዎች በአንዱ እንኳ አልቀጣችሁም፤ ፈዋሻችሁ እኔ እግዚአብሔር ነኝ፡፡”

2) ኢየሱስ ህመምተኞችን እጅ ጭኖ ፈወሳቸው፡፡

● ማር.6÷56

56. ኢየሱስም በየሄደበት ስፍራ ሁሉ በመንደር፣ በከተማ፣ በገጠርም ሕመምተኞችን በየአደባባዩ እያስቀመጡ የልብሱን ጫፍ እንኳ ለመንካት ይለምኑት ነበር፣ የነኩትም ሁሉ ይድኑ ነበር፡፡

3) ኢየሱስ የእኛን ድካም በመውሰድ ህመማችንን ተቀበለ፡፡

● ማቴ.8÷17

17. ይህ በነቢዩ ኢሳይያስ እንዲህ ብሎ የተናገረው ትንቢት ተፈጸመ፤ "እርሱ ሕመማችንን ተቀበለ፤ ደዌያችንንም ተሸከመ"

4) ኢየሱስ በጅራፍ ተመትቶ እኛን ፈወሰ፡፡

● ኢሳ.53÷5

5-እርሱ ግን ስለ መተላለፋችን ቈሰለ፥ ስለ በደላችንም ደቀቀ የደኅንነታችንም ተግሣጽ በእርሱ ላይ ነበረ፥ በእርሱም ቍስል እኛ ተፈወስን።

5) ለህመምተኛ እጅ በመጫን መፈወስ ይቻላል፡፡

● ማር.16÷18

18. እባቦች ቢይዙ፤ ወይም የሚገድል መርዝ እንኳ ቢጠጡ አይጐዳቸውም፤ እጃቸውን በበሽተኞች ላይ ይጭናሉ እነርሱም ይድናሉ፡፡"

6) የእምነት ፀሎት ህመምተኞችን ያድናል፡፡

● ያዕ.5÷15

15-እንዲህ ዐይነቱ በእምነት ላይ የተመሠረተ ጸሎት በሽተኛውን ያድነዋል፤ ጌታም ከበሽታው ይፈውሰዋል፤ የሠራው ኃጢአትም ቢኖር ይቅር ይባልለታል፡፡

3. ስለ ፈውስ መሰረታዊ ሁኔታዎች፡-

1) ከኃጢአታቸው ነፃ መውጣት::

● 1ዮሐ.1÷9

9-ኃጢአታችንን ለእግዚብሔር ብንናዘዝ እርሱ ታማኝና ጻድቅ ስለ ሆነ ኃጢአታችንን ሁሉ ይቅር ይልልናል፤ ከበደላችንም ሁሉ ያነጻናል፡፡

2) በተስፋ ቃል መመካት፡፡

● ያዕ.5÷14

14-ከእናንተ መካከል የታመመ ሰው ቢኖር የቤተ ክርስቲያን ካህናትን (ሽማግሌዎችን) ወደ እርሱ ይጥራ፤ እነርሱም በሽተኛውን በጌታ በኢየሱስ ክርስቶስ ስም ዘይት ቀብተው ይጸልዩለት፡፡

3) በፍቅር ጌታ ማመን፡፡

● ሉቃ.4÷18-19

18. "የጌታ መንፈስ በእኔ ላይ ነው፣ ለድኾች ወንጌልን እንድሰብክ፣ እግዚአብሔር እኔን ቀብቶኛልና፤ ለታሰሩት መፈታትን፣ ለዕውሮች ማየትን እንዳውጅና የተጨቈኑትንም ነጻ እንዳወጣ ልኮኛል፣

19. እንዲሁም ጌታ ሕዝቡን የሚያድንበትን የጸጋ ዓመት እንዳስታውቅ ልኮኛል፡፡"

4) በልብ ውሳኔ እስከ መጨረሻ ድረስ በጌታ መመካት

● ማር.10÷46-48

46. ከዚህ በኋላ ወደ ኢያሪኮ መጡ፡፡ ኢየሱስና ደቀ መዛሙርቱ ከብዙ ሕዝብ ጋር ከኢያሪኮ ሲወጡ ዐይነ ሰውሩ የጤሜዎስ ልጅ በርጤሜዎስ በመንገድ ዳር ተቀምጦ ይለምን ነበር፡፡

47. እርሱም የናዝሬቱ ኢየሱስ መሆኑን በሰማ ጊዜ፣ "የዳዊት ልጅ፣ ኢየሱስ ሆይ፣ ማረኝ!" እያለ ይጮኽ ጀመር፡፡

48. ብዙዎቹ፣ "ዝም በል!" ብለው ገሠጹት፣ እርሱ ግን "የዳዊት ልጅ ሆይ! ማረኝ!" እያለ ይበልጥ ጮኸ፡፡

4. የፈውስ መንገድ

1) በመጀመሪያ መንፈሳዊ ሕይወት እንዲፈውስ ማድረግ

በኢየሱስ ክርስቶስ ስም እንዲያምኑ ማድረግ፡፡

● ዮሐ.1÷12

12. ነገር ግን ኢየሱስ ራሱ ለተቀበሉትና በስሙ ላመኑት ሁሉ ሰዎች የእግዚአብሔር ልጆች የመሆን መብት ሰጣቸው፡፡

● 3ዮሐ.1÷2

2-ወዳጄ ሆይ! ኑሮህ ሁሉ እንዲሳካልህ፣ ጤንነት እንዲኖርህና እንዲሁም የመንፈስ እርካታ እንድታገኝ እመኝልሃለሁ፡፡

2) በንስሐ ወደ እግዚአብሔር ፊት መቅረብ

● ያዕ.5÷13-16

13-ከእናንተ መካከል ችግር የደረሰበት ሰው ቢኖር ይጸልይ፤ ደስ ያለው ሰውም ቢኖር እግዚአብሔርን በማመስገን ይዘምር፡፡

14-ከእናንተ መካከል የታመመ ሰው ቢኖር የቤተ ክርስቲያን ካህናትን (ሽማግሌዎችን) ወደ እርሱ ይጥራ፤ እነርሱም በሽተኛውን በጌታ በኢየሱስ ክርስቶስ ስም ዘይት ቀብተው ይጸልዩለት፡፡

15-እንዲህ ዐይነቱ በእምነት ላይ የተመሠረተ ጸሎት በሽተኛውን ያድነዋል፤ ጌታም ከበሽታው ይፈውሰዋል፤ የሠራው ኃጢአትም ቢኖር ይቅር ይባልለታል፡፡

16-ስለዚህ እንድትፈወሱ ኃጢአታችሁን እርስ በርሳችሁ ተናዘዙ፤ እያንዳንዱም ለሌላው ይጸልይ፤ የጻድቅ ሰው ጸሎት ብዙ ውጤት የሚያስገኝ ታላቅ ኀይል አለው፤

3) በወንጌል መፈወስ

በኢየሱስ ስም ስንታዘዝ ህመምተኞች ይፈወሳሉ፡፡

● ሮሜ.1÷16

16. እኔ በወንጌል ቃል አላፍርም፤ ምክንያቱም ለሚያምን ሁሉ ለድነት የማሆን የእግዚአብሔር ኀይል ነው፤ ይህም በመጀመሪያ ለአይሁድ፣ ቀጥሎም ለአሕዛብ ነው፡፡

4) ለቃሉና ለፀሎት ልምምድ ማድረግ ያስፈልጋል፡፡

● 1ጢሞ.4÷5

5-በእግዚአብሔር ቃልና በጸሎት የተቀደሰ ይሆናል፡፡

5) የነፍሳችንን ሰላምና የመንፈስ ቅዱስን ሥልጣን እንደ ጋሻ መያዝ፡፡

● ኤፌ.6÷14-17

14-እንግዲህ እውነትን እንደ ዝናር በወገባችሁ ታጥቃችሁ፥ ጽድቅን እንደ ጥሩር ለብሳችሁ፥

15-የሰላምን ወንጌል እንደ ጫማ በእግሮቻችሁ ተጫምታችሁ በመዘጋጀት ቁሙ፡፡

16-ከዚህም ሁሉ በላይ እንደ እሳት የሚንበለበሉትን የዲያብሎስን ፍላጻዎች ሁሉ ማጥፋት የምትችሉበትን እምነት እንደ ጋሻ አንግቡ፡፡

17-መዳንን እንደ ራስ ቊር በራሳችሁ ላይ ድፉ፤ እንዲሁም ከመንፈስ ቅዱስ የሚገኘውን ሰይፍ ይኸውም የእግዚአብሔርን ቃል ያዙ፡፡

5. ከፈውስ በኃላ መንፈሳዊ ሕይወቱን መጠበቅ አስፈላጊ ነው፡፡

1) የተፈውሱትን ሰዎች በመድረኩ ፊት ለፊት ማስቀመጥ፡፡

2) ፀሎት እስትንፋስ ነው (ፀሎትን እንድፀልዩ) ማድረግ፡፡

3) በቃሉ ጠንክረው እንዲቆሙ ማድረግ፡፡

4) በክርስቲያኖች ህብረት እንዲደሰቱ ማድረግ፡፡

5) የምስክርነት ሕይወት እንድኖር ማድረግ፡፡

6) እግዚአብሔርን በማመስገን ሰላምን ተቀብለው እንዲለማመዱ ማድረግ፡፡

በጌታ ምሪት የፈውስ አገልግሎት እንደምናከናውን አውቀህ፤ ህመምተኞችን ስታገኝ በጌታ ላይ ብቻ በመመካት ጠንካራ ፈውስ እንደሚጀምር መግለፅ፡፡

★ መንፈሳዊ ሕይወታችን የሚታነጽበት መንገድ

① በንስሐ

② ኢየሱስ ክርስቶስን በማመን

③ እግዚአብሔርን በማመን

④ በምስጋና ሕይወት በመኖርና ዘውትር ኢየሱስ ክርስቶስን በትክክል በመታዘዝ፡፡

★ ፈውስ እንድታዘዝልን ደጋግሞ መጸልይ

① በኢየሱስ ክርስቶስ ስም አዝሃለሁ አንተ በሽታ ውጣ!

② እኔ በኢየሱስ ስምና በመንፈስ ቅዱስ ሥልጣን አዝሃለሁ በጉልበቱ ላይ ያለህ ህመም ውጣ!

③ በናዝሬቱ በኢየሱስ ስም አዝሃለሁ ራስምታት ውጣ!

④ እኔ በኢየሱስ አዘዝኩት አንተ ጉንፋን ከእኔ ውጣ!

⑤ በጌታ በኢየሱስ ክርስቶስ ስም ፀለይኩ ይህን ፈውስ ስጥ!

ምዕራፍ አስር

10. ኢየሱስ ክርስቶስን ካመንህ በኃላ ለምን አዘንህ? (ዕብ.11÷1)

● ዕብ.11÷1

1-እምነት ማለት በተስፋ የሚጠበቀውን ነገር፣ "አዎን፣ በእውነት ይሆናል" ብሎ መቀበል ነው፤ በዐይን የማይታየውንም ነገር እንደሚታይ አድርጎ መቍጠር ነው፡፡

አንድ ቀን ሰይጣን ዕቃዎቹን ይሸጣል፡፡ ከእቃዎቹም መካከል አንዳንዶቹ፡-ጭንቀት፣ ፍርሃት፣ ምኞት፣ ልቅሶ፣ ኩራት (ትዕቢት) ወዘተ… እነዚህን ነገሮች ለክፉ መላእክት ይሸጣል፡፡ ነገር ግን በሚሸጠው ዕቃ ላይ በፅሁፍ [2]ይህ ዕቃ አይሸጥም[2] ብሎ ይፅፋል፡፡ ክፉ መላዕክ ይህ ዕቃ ለምን አይሸጥም ብሎ ሲጠይቅ ሰይጣን መልሶ ሌሎች ዕቃዎች ብዙ ናቸው ይህ ግን ትንሽ ስለሆነ ነው አለ፡፡ ያ ዕቃ ምንድን ነው? ሰይጣን የዕቃውን ዓይነት ሲገልጽ ሐዘን ነው አለ፡፡ ሐዘን ሲገባ ሰይጣን ሥራ ይጀምራል፡፡ ሐዘን ሲገባ መልካም ራዕይ ይጠፋል፡፡ ተስፋ መቁረጥ፣ የሥራ ማጣት ሁሉ ይከሰታል፡፡

★ ለምን በእምነት ላይ ተወራርዶ ይመጣል?

① ተልዕኮ ስለጠፋ ነው። በሰዎች ውስጥ የኅብረት ችግር ስላለ የእግዚአብሔርን የጸጋ ስጦታና ሥልጣን ይጠፋል።

② የዓለም ደስታ በዓይን ስለምመጣ::

③ እንደ ራሱ አካባቢ በሃዘን ልመታ።

④ ከክፉ መንፈስ መግዛት ይመጣል:: ክፉውን ቃል።

1. ኢየሱስን ካመንህ በኃላ ለምን አሳዘንህ?

1) ችግሮችና ስቃይ ስለደረሰ፡፡ የሰጥያን እልማት ሰዎች እንዲጨነቁ ነው፡፡

● 1ጴጥ.5÷7-8

7-እርሱ ለእናንተ ስለሚያስብ የማያስጨንቃችሁን ሐሳብ ሁሉ በእርሱ ላይ ጣሉት፡፡

8-በመጠን ኑሩ፤ ንቁም! ጠላታችሁ ዲያብሎስ የሚውጠውን በመፈለግ እንደሚያገሣ አንበሳ በዙሪያችሁ ይንጐራደዳል፡፡

2) የእግዚአብሔርን ሥልጣን ባለማወቀ።

● ማቴ.12÷28-29

28. ነገር ግን እኔ በእግዚአብሔር መንፈስ አጋንንትን የማስወጣ ከሆነ፣ እንግዲህ የእግዚአብሔር መንግሥት በእናንተ ላይ መጥታለች ማለት ነው፡፡

29. ደግሞስ አንድ ሰው አስቀድሞ ኀይለኛውን ሳያስር ወደ ኀይለኛው ቤት ገብቶ ንብረቱን መዝረፍ እንዴት ይችላል? ኀይለኛውን ካሰረ በኋላ ቤቱን መበዝበዝ ይችላል፡፡

3) የእግዚአብሔርን ቃል በሕይወቱ ባለመለማመድ፡፡

ልባችን መልካም እርሻ ላይ እንደተዘራ ዘር፤ በትዕግስት ፀንቶ ፍሬ የሚያፈራ ሊሆን ይገባል፡፡ ቶሎ ቶሎ መሥራት በጠላት ወጥመድ ውስጥ ያስገባል፡፡

● ሉቃ.8÷15

15. በመልካም መሬት ላይ የወደቀው ዘር፤ በመልካምና በቅን ልብ የእግዚአብሔርን ቃል ሰምተው የሚጠብቁ ሰዎች ይመሰላል ናቸው፣ እነርሱ በቃሉ ጸንተው ፍሬ የሚያፈሩ ናቸው፡፡”

4) በልብህ ውስጥ ማን አለ? በልብህ ውስጥ መንፈስ ቅዱስ ሊኖር ይገባል፡፡

● ሮሜ 8÷5-6

5-በሥጋ ፈቃድ የሚኖሩ ሥጋዊ ነገር፣ በመንፈስ ፈቃድ የሚኖሩ ግን መንፈሳዊውን ነገር ያስባሉ፡፡

6-ሥጋዊ ነገር ማሰብ ሞትን ያመጣል፤ መንፈሳዊ ነገር ማሰብ ግን ሕይወትንና ሰላምን ይሰጣል፡፡

5) ሰዎች ወደ ቤተክርስቲያን ብቻ ስለሚሄዱ

በሕይወታቸው ኢየሱስ ክርስቶስን ሳያምኑ ለሰዎች የቤተክርስቲያን ደንበኛ ሆኖ እንዲኖር ስለሚያደርግ፡፡

● ማቴ12÷43-45

43. ቀጥሎም ኢየሱስ እንዲህ አለ፣ “ርኩስ መንፈስ ከሰው በወጣ ጊዜ የሚያርፍበት ቦታ በመፈለገ ውሃ በሌለበት በደረቅ ቦታ ይዞራል፡፡ ነገር ግን አያገኝም፣

44. ርኩስ መንፈስ እንዲህ አለ፡፡ ‘እኔ ወደ ወጣሁበት ቤት ተመልሼ ልሂድ’ ይላል፤ ወደ ቤቱ ተመልሶ ሲመጣ፤ ቤቱ ባዶ ሆኖ፤ ጸድቶ፤ ተዘጋጅቶ ያገኘዋል፡፡

45. ከዚህ በኋላ፤ ርኩስ መንፈስ ይሄድና ከእርሱ ይባስ የከፉትን ሌሎች ሰባት አጋንንት ይዞ ይመጣል፡፡ እነርሱም ሰውየው ውስጥ ገብተው ይኖራሉ፡፡ የዚያም ሰው የኋለኛው ሁኔታ ከፊተኛው የከፋ ይሆናል፡፡ በዚህ ክፉ ትውልድ ላይም እንዲሁ ይሆንበታል፡፡”

2. የእግዚአብሔርን ባህረይ መለማመድ በጣም አስፈላጊ ነው፡፡

1) እግዚአብሔርን ማግኘት ያስፈልጋል፡፡ የዘላለም ሕይወት የሚሆነውን ኢየሱስን ማመን ማለት ነው፡፡

● ዮሐ.17÷3

3. የዘለዓለም ሕይወትም አንተ ብቻ እውነተኛውን አምላክና የላክኸውን ኢየሱስ ክርስቶስን ማወቅ ነው፡፡

2) ኢየሱስን እንደ ግል አዳኝና ጌታ አድርገው መቀበል፡፡

● ዮሐ.1÷12

12. ነገር ግን ኢየሱስ ራሱ ለተቀበሉትና በስሙ ላመኑት ሰዎች ሁሉ የእግዚአብሔር ልጆች የመሆን መብት ሰጣቸው፡፡

3) ወዲያውኑ ለቀድሞ ችግሮች፤ለአሁኑ ችግሮችና ለወደፊት ችግሮች ኢየሱስ ክርስቶስ መፍትሄ እንደሚሰጥ ማመን፡፡

● ኤፌ2÷3-7

3-እኛም ሁላችን ከዚህ በፊት በእነርሱ መካከል የሥጋችንን ፈቃድና የአእምሮአችንን ሐሳብ እየተከተልን በሥጋችን ምኞት እንኖር ነበር፤ እንደ ሌሎቹም በተፈጥሮአችን በእግዚአብሔር ቊጣ ሥር ነበርን፡፡

4-ነገር ግን የእግዚአብሔር ምሕረቱ ብዙ ከመሆኑና ለእኛም ያለው ፍቅር ታላቅ ከመሆኑ የተነሣ፤

5-በበደላችን የሞትን ብንሆንም እንኳ እግዚአብሔር ከክርስቶስ ጋር እንድንኖር አድርጎናል፤ እናንተም የዳናችሁት በጸጋው ነው፡፡

6-እግዚአብሔር በክርስቶስ ኢየሱስ አማካይነት ከእርሱው ጋር ከሞት አስነሥቶ በሰማያዊ ስፍራ ከእርሱ ጋር አስቀመጠን፡፡

7-ይህንንም ያደረገው በኢየሱስ ክርስቶስ ለእኛ የገለጠውን ቸርነትና ወደር የሌለውን የጸጋውን ብልጽግና በሚመጡት ዘመናት ሊያሳየን ብሎ ነው፡፡

4) በተከታታይ በረከት ውስጥ መኖር

- ኤፌ.2÷7

7-ይህንንም ያደረገው በኢየሱስ ክርስቶስ ለእኛ የገለጠውን ቸርነትና ወደር የሌለውን የጸጋውን ብልጽግና በሚመጡት ዘመናት ሊያሳየን ብሎ ነው፡፡

5) አሁን አንተ ለራስህ መኖር ሳይሆን ኢየሱስ ክርስቶስ በአንተ ውስጥ ይኖራል፡፡

- ገላ.2÷20

20-እኔ ከክርስቶስ ጋር እንደ ተሰቀልኩ ያኽል ስለምቈጥር ከእንግዲህ ወዲህ ክርስቶስ በእኔ ውስጥ ይኖራል እንጂ እኔ ለራሴ ሕይወት የምኖር አይደለሁም፤ አሁንም በሥጋዊ አካሌ የምኖረው በወደደኝና ስለ እኔ ራሱን አሳልፎ በሰጠው በእግዚአብሔር ልጅ በማመን በተገኘው ሕይወት ነው፡፡

6) የመንፈስ ቅዱስ ምሪት መቀበል፡፡ የቃል፣ድምፅ፣ሰላም፣ተስፋ ህልምና ራዕይ ከመንፈስ ቅዱስ መቀበል፡፡

- ዮሐ.14÷26-27

26. አብ በእኔ ስም የሚልከው አጽናኙ መንፈስ ቅዱስ ግን ሁሉን ነገር ያስተምራችኋለሁ፣ እኔ የነገርኳችሁንም ሁሉ እንድታስታውሱ ያደርጋችኋል፡፡

27. “ሰላምን እተውላችኋለሁ፣ ሰላሜንም እሰጣችኋለሁ፣ እኔ የምሰጣችሁ ሰላም ዓለም እንደሚሰጠው ዐይነት አይደለም፣ ልባችሁ አይጨነቅ፣ ደግሞም አይፍራ፡፡

7) የመንፈስ ቅዱስ ፍሬ መብዛት

እኔ ሳልሆን በእኔ ውስጥ የሚኖረው መንፈስ ቅዱስ ሥራውን ይሠራል፡፡

- ሐዋ.2÷1-13

1-የበዓለ ኀምሳ ቀን በደረሰ ጊዜ ደቀ መዛሙርቱ ሁሉ በአንድነት በአንድ ቦታ ተሰብስበው ነበር፤

2-ድንገትም እንደ ብርቱ ዐውሎ ነፋስ ያለ ድምፅ ከሰማይ መጥቶ ተቀምጠው የነበሩበትን ቤት ሞላው፡፡

3-የእሳት ነበልባሎች የሚመስሉ ልሳኖች ታዩአቸው፤ ተከፋፍለውም በእያንዳንዳቸው ላይ አረፉባቸው፡፡

4-ሁሉም በመንፈስ ቅዱስ ተሞሉ፤ መንፈስ ቅዱስ እንዲናገሩ በሰጣቸው ችሎታ መጠን በሌሎች ቋንቋዎች መናገር ጀመሩ፡፡

5-በዚህ ጊዜ በዓለም ካሉት አገሮች ሁሉ የመጡ፣ በጸሎት የተጉ አይሁድ በኢየሩሳሌም ይኖሩ ነበር፡፡

6-ይህንንም ድምፅ በሰሙ ጊዜ ብዙ ሰዎች ተሰበሰቡ፤ ለሚያምኑ በገዛ ቋንቋው ሲናገሩ ስለ ሰሙአቸው ተደነቁ፡፡

7-እነርሱ በመገረምና በመደነቅም እንዲህ አሉ፤ "እነሆ፣ እነዚህ እንዲህ የሚናገሩት ሁሉ የገሊላ ሰዎች አይደሉምን?

8-ታዲያ፣ እኛ የትውልድ አገራችን ቋንቋ ሲናገሩ የምንሰማቸው እንዴት ነው?

9-እኛ በጳርቴ፣ በሜድ፣ በዔላም፣ በመስጴጦምያ፣ በይሁዳ፣ በቀጰዶቅያ፣ በጳንጦስ፣ በእስያ፣

10-በፍርግያ፣ በጵንፍልያ፣ በግብጽ፣ በቀሬና አጠገብ ባሉት በሊቢያ አውራጃዎች የምንኖር ነን፤ ከሮምም ከሮም የመጣን፣

11-አይሁድና ወደ ይሁዲነት የገባን እንገኛለን፤ የቀርጤስና የዓረብ ሰዎች ይገኛሉ፤ እኛ እነዚህ የእግዚአብሔርን ታላቅ ሥራ በየቋንቋችን ሲናገሩ እንሰማቸዋለን"

12-ሁሉም ተገረሙና አመንትተው እርስ በርሳቸው፣ "ይህ ነገር ምን ይሆን!" ተባባሉ፡፡

13-አንዳንዶቹ ግን "አዲስ የወይን ጠጅ ጠጥተው ሰክረዋል!" እያሉ አፌዙባቸው፡፡

3. በፈተና እንዳንወድቅ በየቀኑ መጽናት ያስፈልጋል፡፡

1) ጌታ ኢየሱስ ክርስቶስ የሚመጣበት ቀን ስለተቃረበ፡፡

- ሮሜ.13÷11-14

11. እንግዲህ ከእንቅልፍ የምትነቁበት ሰዓት አሁን መድረሱን ዕወቁ፤ በፊት ካመንበት ጊዜ ይልቅ አሁን የምንድንበት ቀን ይበልጥ ወደ እኛ ቀርቦአል፡፡

12. ሌሊቱ እያለፈ ነው፤ ቀኑም ቀርቦአል፤ ስለዚህ በጨለማ የሚሠራውን ሥራ እንተው፤ የብርሃንን የጦር መሣሪያ እንልበስ፡፡

13. በቀን እንደ ምንመላለስ በአገባብ እንመላለስ፡፡ በጭፈራና በስካር አይሁን፤ በዝሙትና በመዳራት አይሁን፤ በክርክርና በቅናትም አይሁን፡፡

14. ስለዚህ ጌታ ኢየሱስ ክርስቶስን ልበሱት እንጂ የሥጋችሁን ፍላጎት ለማርካት አታስቡ፡፡

2) ጠላታችን ሰይጣን እንደ አንበሳ በዙሪያችን እኛን ለመጣል ስለሚያገሳ

- 1ጴጥ.5÷8

8-በመጠን ኑሩ፤ ንቁም! ጠላታችሁ ዲያብሎስ የሚውጠውን በመፈለግ እንደሚያገሣ አንበሳ በዙሪያችሁ ይንጐራደዳል፡፡

3) የባጠግነት ፈተና ከእምነት ስለሚያወጣን ሊንጠነቀቅ ያስፈልጋል::

ገንዘብና ንብረት በሰው ቁጥጥር ሥር መሆን ያስፈልጋል፡፡ ነገር ግን ገንዘብ ሰዎችን የሚቆጣጠር ከሆነ እነዚያ ሰዎች ከእግዚአብሔር መንገድ በቀላሉ ስተዋል፡፡ ጥሩ ሰው ሆኖ ለመኖር የመንፈስ ቅዱስ ልምምድ ያስፈልጋል፡፡ በተጨማሪ መንፈስ ቅዱስ ሰዎችን የሚገዛ ነው፡፡ የመንፈስ ቅዱስ ሥልጣን ያለው ሰው ገንዘብን በአግባቡ የሚይዝ ሰው ነው፡፡

- 1ጢሞ.6÷10

10-ይህም የሚሆነው የገንዘብ ፍቅር የክፋት ሁሉ ምንጭ ስለሆነ ነው፡፡

4) ሰይጣን እኛን ለመስረቅ ለመግደልና ለማጥፋት ሁልጊዜ ይፈልጋል።

- ዮሐ.10÷10

10. ሌባው ሊሰርቅ፣ ሊገድልና ሊያጠፋ ብቻ ይመጣል፣ እኔ የመጣሁት በጎቼ ሕይወት እንዲያገኙና የተትረፈረፈ ሕይወት እንዲኖራቸው ነው፡፡

4. መንፈስ ቅዱስ የመንፈስን ፍሬዎች ይጨምራል፡፡

1) እምነትና ጽድቅ ይመጣል

● ሐዋ.2÷1-17

የበዓለ ኀምሳ ቀን በደረሰ ጊዜ ደቀ መዛሙርቱ ሁሉ በአንድነት በአንድ ቦታ ተሰብስበው ነበር፤

ድንገትም እንደ ብርቱ ዐውሎ ነፋስ ያለ ድምፅ ከሰማይ መጥቶ ተቀምጠው የነበሩበትን ቤት ሞላው፡፡

የእሳት ነበልባሎች የሚመስሉ ልሳኖች ታዩአቸው፤ ተከፋፍለውም በእያንዳንዳቸው ላይ አረፉባቸው፡፡

ሁሉም በመንፈስ ቅዱስ ተሞሉ፤ መንፈስ ቅዱስ እንዲናገሩ በሰጣቸው ችሎታ መጠን በሌሎች ቋንቋዎች መናገር ጀመሩ፡፡

በዚህ ጊዜ በዓለም ካሉት አገሮች ሁሉ የመጡ፣ እግዚብሔርን በጸሎት የተጉ አይሁድ በኢየሩሳሌም ይኖሩ ነበር፡፡

ይህንንም ድምፅ በሰሙ ጊዜ ብዙ ሰዎች ተሰበሰቡ፤ ለሚያምኑ በገዛ ቋንቋው ሲናገሩ ስለ ሰሙአቸው ተደነቁ፡፡

እነርሱ በመገረምና በመደነቅም እንዲህ አሉ፤ “እነሆ፣ እነዚህ እንዲህ የሚናገሩት ሁሉ የገሊላ ሰዎች አይደሉምን?

ታዲያ፣ እኛ የትውልድ አገራችንን ቋንቋ ሲናገሩ የምንሰማቸው እንዴት ነው?

እኛ በጳርቴ፣ በሜድ፣ በዔላም፣ በመስጴጦምያ፣ በይሁዳ፣ በቀጰዶቅያ፣ በጳንጦስ፣ በእስያ፣

በፍርግያ፣ በጵንፍልያ፣ በግብጽ፣ በቀሬና አጠገብ ባሉት በሊቢያ አውራጃዎች የምንኖር ነን፤ ከሮምም ከሮም የመጣን፣

አይሁድና ወደ ይሁዲነት የገባን እንገኛለን፤ የቀርጤስና የዓረብ ሰዎች ይገኛሉ፤ እኛ እነዚህ የእግዚአብሔርን ታላቅ ሥራ በየቋንቋችን ሲናገሩ እንሰማቸዋለን”

ሁሉም ተገረሙና አመንትተው እርስ በርሳቸው፣ “ይህ ነገር ምን ይሆን!” ተባባሉ፡፡

አንዳንዶቹ ግን “አዲስ የወይን ጠጅ ጠጥተው ሰክረዋል!” እያሉ አፌዙባቸው፡፡

በዚያን ጊዜ ጴጥሮስ ከዐሥራ አንዱ ጋር ቆመና ድምፁን ከፍ አድርጎ ለሕዝቡ እንዲህ ሲል ተናገረ፣ “እናንተ የይሁዳ ሰዎችና የኢየሩሳሌም የምትኖሩ ሁሉ፣

*ይህ የሆነው ነገር በእናንተ ማወቅ ዘንድ ይታወቀ ይሁን፣ ንግግሬን አድምጡኝ፡፡*

*አሁን ገና ከጠዋቱ ሶስት ሰዓት ስለ ሆነ፣ እናንተ እንዳሰባችሁት እነዚህ ሰዎች አልሰከሩም፡፡*

*ነገር ግን ይህ የሆነው ነቢዩ ኢዩኤል እንዲህ ሲል የተናገረው ቃል እንዲፈጸም ነው፤*

*እግዚአብሔር በመጨረሻው ቀን እንዲህ ይሆናል ይላል፤ 'እኔ መንፈሴን በሰው ሁሉ ላይ አፈሳለሁ፤ ወንዶችና ሴቶች ልጆቻችሁ ትንቢት ይናገራሉ፤ ጐልማሶቻችሁም ራእይ ያያሉ፤ ሽማግሌዎቻችሁም ሕልም ያልማሉ፡፡*

2) *ሥልጣንን ይጨምራል፡፡*

- *ሐዋ*.3÷1-10

*አንድ ቀን ጴጥሮስና ዮሐንስ በጸሎት ጊዜ ከቀኑ በዘጠኝ ሰዓት ወደ ቤተ መቅደስ ይወጡ ነበር፡፡*

*እዚያ "ውብ" እየተባለ የሚጠራ በር ነበር፤ ሲወለድ ጀምሮ ሽባ የሆነውን አንድ ሰው ሰዎችን በየቀኑ እያመጡ እዚያ ያስቀምጡት ነበር፤ እርሱ እዚያ ተቀምጦ ወደ ቤተ መቅደስ ከሚገቡት ሰዎች ምጽዋት ይለምን ነበር፡፡*

*ሽባውም ሰውዬ ጴጥሮስና ዮሐንስ ወደ ቤተ መቅደስ ሲገቡ አይቶ ምጽዋት ለመናቸው፡፡*

*ጴጥሮስም ከዮሐንስ ጋር ወደ እርሱ ትኵር ብሎ አየውና፣ "ወደ እኛ ተመልከት" አለው፡፡*

*ሽባውም ሰውዬ ከእነርሱ አንድ ነገር ለማግኘት አስቦ በትኵረት ተመለከታቸው፡፡*

*ጴጥሮስ ግን፣ "እኔ ብርና ወርቅ የለኝም፤ ነገር ግን ያለኝን እሰጥሃለሁ፤ በናዝሬቱ በኢየሱስ ክርስቶስ ስም ተነሥተህ በእግርህ ተመላለስ" አለው፤*

*ቀኝ እጁንም ይዞ አስነሣው፤ ወዲያውኑ እግሩና ቊርጭምጭሚቱ በረታ፡፡*

*ዘሎም ቀጥ ብሎ ቆመ፤ እየተራመደም ከእነርሱ ጋር ወደ ቤተ መቅደስ ገባ፤ እየተራመደና እየዘለለም እግዚብሔርን ያመሰግን ነበር፡፡*

*ሕዝቡም ሁሉ እየተራመደና እግዚአብሔርን እያመሰገነ ሲመላለስ ባዩት ጊዜ፣*

“ውብ በር” እየተባለ በሚጠራው በቤተ መቅደሱ በር አጠገብ ተቀምጦ ምጽዋት ይለምን የነበረው እርሱ መሆኑን ዐወቁ፤ ሕዝቡ በእርሱ ላይ ከተፈጸመውም ነገር የተነሣ በመደነቅና በመገረም ተሞሉ፡፡

3) ጠንካራ ስብከት ይጨምራል፡፡

● ሐዋ.4÷19-20

19-ጴጥሮስና ዮሐንስ ግን እንዲህ ሲሉ መለሱላቸው፣ “እኛ ከእግዚአብሔር ይልቅ ለእናንተ መታዘዝ በእግዚአብሔር ፊት ተገቢ ነውን? እስቲ እናንተ ራሳችሁ ፍረዱ፡፡

20-እኛስ ያየነውንና የሰማነውን ከመናገር አንቈጠብም፡፡”

4) በችግሮች ላይ ድልን ይሰጣል፡፡

● ሐዋ.12÷1-5

በዚያን ዘመን ንጉሥ ሄሮድስ አንዳንድ የቤተ ክርስቲያን ሰዎችን ማሳደድ ጀመረ፤

ሄሮድስ የዮሐንስን ወንድም ያዕቆብን በሰይፍ አስገደለው፡፡

ሄሮድስ ይህ ነገር አይሁድን ደስ እንዳሰኛቸው ባየ ጊዜ ጴጥሮስንም ደግሞ አስያዘው፤ ይህም የሆነው አይሁድ የቂጣ በዓልን የሚያከብሩባቸው ቀኖች ነበር፡፡

ሄሮድስ ጴጥሮስን ካስያዘ በኋላ ወደ ወህኒ ቤት አስገባው፤ አራት አራት ወታደሮች ሆነው እንዲጠብቁት ለአራት ጭፍሮች አስረከበው፤ የፋሲካ በዓል ካለፈ በኋላ ሕዝብ ፊት አውጥቶ ሊያስፈርድበት አስቦ ነው፡፡

ስለዚህ ጴጥሮስ በወህኒ ቤት ተይዞ ይጠበቅ ነበር፤ ነገር ግን ቤተ ክርስቲያን ስለ እርሱ ወደ እግዚአብሔር በጥብቅ ትጸልይ ነበር፡፡

5) ስለተልዕኮ የራሳቸውን ነፍስ እንዲሰጡ ያደርጋል፡፡

● ሐዋ.20÷24

24-የእግዚአብሔርን የጸጋ ወንጌል ለማስተማር ከጌታ ከኢየሱስ የተቀበልሁትን የማገልገል ግዴታ ብፈጽም፣ ለእኔ ሕይወቴ ከምንም እንደማይቈጠር እንደ ከንቱ ነገር ናት፡፡

6) ለዓለም ሚስዮን በር ይከፍታል፡፡ መንፈስ ቅዱስ ስመጣ ወንጌልን እንድሰብኩ ቃል ይሰጣቸዋል፡፡

● ሐዋ.13÷2-7

2-እነርሱ ጌታን እያመለኩና እየጾሙ ሳሉ፣ መንፈስ ቅዱስ፣ “በርናባስንና ሳውልን እኔ ለጠራኋቸው ሥራ ለዩልኝ” አለ፡፡

3-እነርሱም ከጾሙና ከጸለዩ በኋላ እጃቸውን ጭነው ላኳቸው፡፡

4-በርናባስና ሳውልም በመንፈስ ቅዱስ ተልከው ወደ ሴሌውቅያ ወረዱ፤ ከዚያም በመርከብ ወደ ቆጵሮስ ሄዱ፡፡

5-እነርሱ ወደ ሰላሚስ ከተማ በደረሱ ጊዜ በአይሁድ ምኵራቦች የእግዚአብሔርሐን ቃል አስተማሩ፤ ዮሐንስ ማርቆስም ከእነርሱ ጋር ሆኖ ይረዳቸው ነበር፡፡

6-እነርሱ የቆጵሮስን ደሴት አቋርጠው ወደ ጳፉ በደረሱ ጊዜ ባርየሱስ የሚባለውን አንድ አይሁዳዊ ጠንቋይ አገኙ፤ እርሱ ሐሰተኛ ነቢይ ነበር፡፡

7-ባርየሱስም ሰርግዮስ ጳውሎስ ከተባለው አስተዋይ አገረ ገዥ ጋር ነበረ፡፡ ይህ አገረ ገዥ፣ የእግዚአብሔርን ቃል ለመስማት ፈልጎ በርናባስንና ሳውልን አስጠራቸው፡፡

5. በመንፈሱ ሚማረክ እግዚአብሔር በሚሰጠው መልካም በረከት ውስጥ ይኖራል፡፡

1) ኢየሱስ ሲያምኑ አካባቢያቸው መልካም ይሆናል

● ሮሜ.5÷17

17. በአንድ ሰው በአዳም ኃጢአት ምክንያት ሞት በሰው ሁሉ ላይ ሥልጣን ካገኘ የእግዚብሔርን የተትረፈረፈ ጸጋና ነጻ ስጦታ ተቀብለው የጸደቁ ሁሉ በአንዱ ሰው በኢየሱስ ክርስቶስ አማካይነት በድል አድራጊነት በሕይወት ይኖራሉ፡፡

2) አካባቢአችን በወንጌል ቢማረክ ሌሎችን ደግሞ እንማረካለን፡፡

● ሐዋ.8÷7 7-ርኵሳን መናፍስት በታላቅ ድምፅ እየጮኹ ከብዙ ሰዎች ይወጡ ነበር፤ ብዙ ሽባዎችና አንካሶችም ተፈወሱ፤

3) በሁሉም ነገር የተትረፈረፈ ሕይወት ይኖራል፡፡

● ዮሐ.10÷10 10. ሌባው ሊሰርቅ፣ ሊገድልና ሊያጠፋ ብቻ ይመጣል፣ እኔ የመጣሁት በጎቼ ሕይወት እንዲያገኙና የተትረፈረፈ ሕይወት እንዲኖራቸው ነው፡፡

4) በአብርሃም በረከት እንድንኖር ያደርጋል፡፡

● ገላ.3÷13-14 13-"በእንጨት ላይ ተሰቅሎ የሚሞት ሁሉ የተረገመ ነው" ተብሎ ስለ ተጻፈ ክርስቶስ ስለ እኛ እንደ ተረገመ ሰው ሆኖ ሕግ ከሚያስከትለው ርግማን ዋጀን፡፡

14-ይህም የሆነው እግዚአብሔር ለአብርሃም የሰጠው በረከት በኢየሱስ ክርስቶስ አማካይነት ለአሕዛብ እንዲደርስና እኛም እግዚአብሔር እሰጣችኋለሁ ያለውን መንፈስ ቅዱስን በእምነት እንድንቀበል ነው፡፡

5) የመንፈስ ቅዱስ ተስፋ እንድንቀበል ያደርጋል፡፡

● ገላ.3÷14 14-ይህም የሆነው እግዚአብሔር ለአብርሃም የሰጠው በረከት በኢየሱስ ክርስቶስ አማካይነት ለአሕዛብ እንዲደርስና እኛም እግዚአብሔር እሰጣችኋለሁ ያለውን መንፈስ ቅዱስን በእምነት እንድንቀበል ነው፡፡

★ የእምነት መሠረት ምንድን ነው?

① ሰዎች እምነታቸውን እንዲያራምዱ ያሉባቸው አካባቢ ይወስናል፡፡

② ለራሱ ብቻ ለሚያምን ሰው ብዙ የግብረ ገብነት ችግር አለው፡፡

③ ክርስቲያን በአካባቢው ጥሩነትና መጥፎነት አይመራም፡፡ ነገር ግን ወደ እግዚአብሔር ይፀልያል፡፡ ወደ እግዚአብሔር የሚፀልይ ሰው ጥሩ ነው፡፡ የኛ መሠረት እግዚአብሔር ብቻ ነው፡፡

ውጤት፡- መልካም ሥራን በመሥራት ብቻ ለመኖር አይሞክሩ በእምነት መኖር ያስፈልጋል፡፡ እግዚአብሔር ብቻ የእኛ መሠረት ስለሆነ እኛን በቃል፣ በሥራ ፣በተልዕኮና በራዕይ ይመራናል፡፡

- ጥሩ ሰው በመጨረሻ ጊዜ ያቋርጣል፡፡ ነገር ግን ክርስቲያን እስከ መጨረሻ ድረስ በክርስትና እየኖረ ቤተክርስቲያንን ይረዳል፡፡

- ሰው የሰውን ፊት ብቻ ያያል፡፡ ነገር ግን እግዚአብሔር የውስጥንና የልብን እምነት ያያል፡፡ ክፍት ስብሰባ የሚሰብክ መሪ አዲስ ሰው ወደ ቤተክርስቲያን መምጣቱን ካየ ከእርሱ ጋር አንድ ላይ በመሆን የእግዚአብሔር ቤት ሥራ ሊሠራ ይገባል፡፡

ምዕራፍ አስር አንድ

11. ቤተክርስቲያን በአንተ የምትደሰትበትን አድርግ

(ለ11 ሳምንት የምታደርገውን ለቤተክርስቲያን ገለፃ ማድረግ ማስታወቅ ያስፈልጋል፡፡)

ቤተክርስቲያን ማለት ምን ማለት ነው? ቤተክርስቲያን የመሄድ ትርጉም ምንድን ነው?

ብዙ ሰዎች ቤተክርስቲያንን የሃይማኖት ሥራ፣ የማህበረሰብ ስብሰባ የሚሰራበት አድርገው ያስባሉ፡፡ ነገር ግን እግዚአብሔር ቤተክርስቲያንን የኢየሱስ ክርስቶስ ማደሪያ ስጋ ነው ይላል፡፡ የክብር ሙሽራ ብሎ ይገልፃል፡፡ እግዚአብሔር በቤተክርስቲያን በኩል ለክርስቲያኖች በረከትን ይሰጣል፡፡ ቤተክርስቲያን ኢየሱስ ክርስቶስን የምታስተዋውቅ ሥፍራ ነው፡፡

★ ስለዚህ ኢየሱስ ክርስቶስን አገኝ

① የኢየሱስ ክርስቶስን ስም መጥራት ያስፈልጋል፡፡

② በኢየሱስ ክርስቶስ ስም መፀለይ ያስፈልጋል፡፡

③ ኢየሱስ ክርስቶስን ጌታና አዳኝ ነው ብሎ በአፉ መመስከር ያስፈልጋል፡፡

ውጤት፡- ኢየሱስ ክርስቶስን ለተቀበለው ሕይወቱ ደስታን ይሰጣል፡፡

- ለኑሮ ችግሮች መፍትሄን ያገኛል

ቤተክርስቲያን ማለት ምን ማለት ነው?

1) የተመረጠ የእግዚአብሔር ሰዎች ስብስብ ነው፡፡

● ኤፌ.1÷23

23-ቤተ ክርስቲያን የክርስቶስ አካል ናት፤ ክርስቶስም በቤተ ክርስቲያንና በሌላውም ሁሉ የሞላ ነው፡፡

2) እግዚአብሔር የሚኖርበት ሥፍራ ነው፡፡

● ኤፌ.2÷22

22-እግዚአብሔር በመንፈሱ የሚያድርበት ሕንጻ ለመሆን እናንተም አብራችሁ በክርስቶስ ትታነጻላችሁ፡፡

3) የእግዚአብሔር ማደሪያ (ቤት) ነው፡፡

● 1ቆሮ.3÷9

9-እኛ ለእግዚአብሔር አብረን የምንሠራ አገልጋዮች ነን፤ እናንተም የእግዚአብሔር እርሻና የእግዚአብሔር ሕንጻ ናችሁ፡፡

4) ክርስቲያኖች የሚያመልኩበት ቦታ ነው፡፡

● መዝ.84÷1-4

1-የሠራዊት አምላክ ሆይ፥ ማደሪያዎችህ እንደምን የተወደዱ ናቸው!

2-ነፍሴ የእግዚአብሔርን አደባባዮች ትወድዳለች ትናፍቅማለች ልቤም ሥጋዬም በሕያው አምላክ ደስ ተሰኘ።

3-ወፍ ለእርስዋ ቤትን አገኘች፥ ዋኖስም ጫጩቶችዋን የምታኖርበት ቤት አገኘች የሠራዊት አምላክ ንጉሤም አምላኬም ሆይ፥ እርሱ መሠዊያህ ነው።

4-በቤትህ የሚኖሩ ሁሉ የተመሰገኑ ናቸው ለዓለምና ለዘላለምም ያመሰግኑሃል።

5) ከእግዚአብሔር ጋር ህብረት የሚያደርግበት ቦታ ነው፡፡

● 1ጴጥ.2÷9

9-እናንተ ግን ከጨለማ ወደሚያስደንቅ ብርሃኑ የጠራችሁን የእግዚአብሔርን አስደናቂ ሥራ እንድታውጁ የተመረጠ ትውልድ፣ የንጉሥ ካህናት፣ እግዚአብሔር ለራሱ ያደረጋችሁ ቅዱስ ሕዝብ ናችሁ፡፡

6) የኢየሱስ ክርስቶስ ሥጋ ማለት ነው፡፡

● ቆላ.1÷18

18-እርሱ አካሉ የሆነችው የቤተ ክርስቲያን ራስ ነው፤ በሁሉ ነገር ቀዳሚ እንዲሆን፤ ከሞት በመነሣትም ፊተኛና መጀመሪያ ነው፡፡

7) የኢየሱስ ክርስቶስ ሙሽራ ናት፡፡ ጌታ ቤተክርስቲያንን እንደ ሙሽራዎች ያያል፤ ቤተክርስቲያን ክርስቲያኖችን ልታንከባክብ ያስፈልጋታል፡፡ የጌታ ዓይኖች ሁልጊዜ በቤተክርስቲያን ላይ ናቸው፡፡

● ማቴ.25÷1

1-"በዚያን ጊዜ መንግሥተ ሰማይ መብራታቸውን ይዘው ሙሽራውን ሊቀበሉ የወጡትን ዐሥር ልጃገረዶች ትመስላለች፡፡

በቤተክርስቲያን በኩል የሚመጣ በረከት ምንድን ነው?

1) በትክክለኛ ቤተክርስቲያን ውስጥ ሲትኖር ለችግሮች መፍትሄን ትሰጣለች፡፡

● መዝ.84÷5-6

5-አቤቱ፥ እርዳታው ከአንተ ዘንድ የሆነለት፥ በልቡም የላይኛውን መንገድ የሚያስብ ሰው ምስጉን ነው።

6-በልቅሶ ሸለቆ ውስጥ በወሰነው ስፍራ የሕግ መምህር በረከትን ይሰጣልና።

2) እውነተኛ ዕረፍትና የሕይወት ተስፋ ትሰጣለች፡፡ ቤተክርስቲያን ሰዎች በነፃነት ወንጌልን እንዲሰሙና እንዲሰብኩ ልታደርግ ይገባታል፡፡

● ማቴ.11÷28-30

28. እናንተ ደካሞች ሸክማችሁ የከበደ ሁሉ ወደ እኔ ኑ፣ እኔም ለእናንተ ዕረፍት አሳርፋችኋለሁ፡፡

29. እኔ በልቤ የዋህና ትሑት ነኝ፣ ቀንበሬን በላያችሁ ተሸከሙ፣ ከእኔም ተማሩ፥ ለነፍሳችሁም ዕረፍት ታገኛላችሁ፤

30. ቀንበሬ ልዝብ ሸክሜም ቀላል ነው፡፡"

3) ለነፍሳት ፈውስን ትሰጣለች፡፡

● ማር.16÷17

17. የሚያምኑትን እነዚህ ምልክቶች ይከተሉአቸዋል፤ በስሜ አጋንንትን ያወጣሉ፣ በአዲስ ቋንቋም ይናገራሉ፣

3) ለህመምተኞች ፈውስ ትሰጣለች፡፡

● ዘፀ.15÷26

26-እንዲህም አላቸው፤ "በጥሞና ትእዛዞቼን ብታዳምጡና በፊቴ መልካም የሆነውን ነገር በታዛዥነት ብታደርጉ፣ ሕጎቼንም ሁሉ ብትጠበቁ፣ በግብጻውያን ላይ ካመጣሁባቸው በሽታዎች በአንዱ እንኳ አልቀጣችሁም፤ ፈዋሻችሁ እኔ እግዚአብሔር ነኝ፡፡"

4) ለቤተሰብ ድነትንና ደስታን ትሰጣለች፡፡

● ሐዋ.16÷31

31-ጳውሎስና ሲላስም፣ "በጌታ በኢየሱስ እመን፤ አንተም ቤተ ሰዎችህም ትድናላችሁ" አሉት፡፡

5) በፀሎት በኩል ለችግሮቻቸው መፍትሄን ታስገኛለች፡፡

● ማር.11÷17

17. እንዲህም ሲል አስተማራቸው፣ "ቤቴ ለሕዝብ ሁሉ የጸሎት ቤት ይባላል!' ተብሎ አልተጻፈምን? እናንተ ግን የሌቦች ዋሻ አደረጋችሁት!"

6) በአብርሃም በረከቶች እንድባረኩ ታደርጋለች፡፡

● ገላ.3÷13-14

13-"በእንጨት ላይ ተሰቅሎ የሚሞት ሁሉ የተረገመ ነው" ተብሎ ስለ ተጻፈ ክርስቶስ ስለ እኛ እንደ ተረገመ ሰው ሆኖ ሕግ ከሚያስከትለው ርግማን ዋጀን፡፡

14-ይህም የሆነው እግዚአብሔር ለአብርሃም የሰጠው በረከት በኢየሱስ ክርስቶስ አማካይነት ለአሕዛብ እንዲደርስና እኛም እግዚአብሔር እሰጣችኋለሁ ያለውን መንፈስ ቅዱስን በእምነት እንድንቀበል ነው፡፡

እግዚአብሔር የቀረፃት ቤተክርስቲያን ሁለት ክንፍ ያላት ቤተክርስቲያን ናት፡፡

1) የትልቅ ቡድን ክንፍ - የቤተክርስቲያን አምልኮ

2) የትንሽ ቡድን ክንፍ - የክፍት ስብሰባ

4. የቤተክርስቲያን ተልዕኮ ምንድን ነው?

1) ለእግዚአብሔር አምልዕኮ ማቅረብ ነው፡፡

● ዮሐ.4÷23

23. ነገረ ግን በእውነት የሚሰግዱ፣ ለአብ በመንፈስና በእውነት የሚሰግዱበት ጊዜ ይመጣል፣ አሁንም መጥቶአል፣ አብም እንደዚህ በእውነት የሚሰግዱለትን ይፈልጋል፡፡

2) ወንጌልን መስበክ ነው፡፡

● ማር.16÷15-16

15. እንዲህም አላቸው፣ "ወደ መላው ዓለም ሂዱ፣ ለሰው ሁሉ ወንጌልን ስበኩ፣

16. ያመነና የተጠመቀ ይድናል፣ የማያምን ግን ይፈረድበታል፡፡

3) ቤተክርስቲያንን ማሳደግ፣ ማስተማርና ልምምድ ማድረግ፡፡

● ኤፌ.1÷11-13

11-ሁሉን ነገር በራሱ ፈቃድ የሚሠራ እግዚአብሔር አስቀድሞ በዐቀደልን መሠረት በክርስቶስ አማካይነት የእርሱ ወገኖች እንድንሆን መረጠን፡፡

12-ይህም የሆነው ክርስቶስን ተስፋ በማድረግ መጀመሪያዎች የሆንነው የእግዚአብሔርን ክብር በምስጋና እንድንገልጥ ነው፡፡

13-እናንተም የመዳናችሁ መልካም ዜና የሆነውን የእውነት ቃል በሰማችሁ ጊዜ በክርስቶስ አምናችኋል፣ እንዲሁም እርሱ ሊሰጣችሁ ተስፋ ባደረገላችሁ በመንፈስ ቅዱስ ታትማችኋል፡፡

4) እያንዳንዱ (እርስበርስ) ማገልገል፡፡

● 1ጴጥ.4÷10

10-የተለያዩትን የእግዚአብሔርን የጸጋ ስጦታዎች በታማኝነት በማስተዳደር ከእናንተ እያንዳንዱ በተሰጠው የጸጋ ስጦታ ሌላውን ያገልግል፡፡

5) ወንጌላዊያንን (ሚሽነሪዎችን) መላክ

● ሐዋ.1÷8

8-ነገር ግን መንፈስ ቅዱስ በእናንተ ላይ በወረደ ጊዜ ኀይልን ትቀበላላችሁ፤ በኢየሩሳሌም፣ በይሁዳ ምድር ሁሉ፣ በሰማርያ፣ እስከ ምድርም ዳርቻ ድረስ ምስክሮቼ ትሆናላችሁ፡፡”

5. እንዴትቤተሰብንቤተክርስቲያንማድረግይቻላል?

1) ኢየሱስን እንዲያምኑ በማድረግ፡፡

● ማቴ.16÷16-18

16. ስምዖን ጴጥሮስም፣ “አንተ ክርስቶስ የሕያው እግዚአብሔር ልጅ ነህ” ሲል መለሰ፡፡

17. ኢየሱስም እንዲህ አለው፣ “የዮና ልጅ ስምዖን ሆይ፣ ብፁዕ ነህ፣ ይህን የገለጠልህ በሰማይ ያለው አባቴ ነው እንጂ ሥጋና ደም አይደለም፡፡

18. እኔም እንዲህ እልሃለሁ፣ አንተ (ጴጥሮስ)፣ አለት ነህ፣ በዚህችም የመሠረት ድንጋይ ላይ ቤተ ክርስቲያኔን እሠራለሁ፣ ይህችንም ቤተ ክርስቲያን የሞት ኀይል እንኳ አያሸንፋትም፡፡

2) ኢየሱስ ክርስቶስን በልባቸው የሕይወታቸው ጌታና አዳኝ አድርገው እንዲቀበሉ በማድረግ፡፡

● ዮሐ.1÷12

12. ነገር ግን ኢየሱስ ራሱ ለተቀበሉትና በስሙ ላመኑት ሰዎች ሁሉ የእግዚአብሔር ልጆች የመሆን መብት ሰጣቸው፡፡

3) የመንፈስ ቅዱስ ቅባት እንዲቀበሉና ለኢየሱስ ሥጋ ብርቱ ሰዎች እንዲሆኑ በማድረግ፡፡

● 1ቆሮ.12÷27

27-እናንተም የክርስቶስ አካል ናችሁ፤ እያንዳንዳችሁም የአካሉ ክፍሎች ናችሁ፡፡

4) በአገልግሎት የኢየሱስ ክርስቶስ አካል የሆኑ ቤተ ክርስቲያን እንዲያድጉ በማድረግ፡፡

● ኤፌ.4÷12

12-ይህንንም ያደረገው የክርስቶስ አካል የሆነችው ቤተ ክርስቲያን እንድትታነጽ፣ ምእመናንን ለክርስቲያናዊ አገልግሎት ለማዘጋጀት ነው፡፡

6. በቤተክርስቲያንበኩልየእግዚአብሔርበረከት፡-

1) የአምልኮ በረከት፡፡

● ዮሐ.4÷24

24. እግዚአብሔር መንፈስ ነው፣ ለእግዚአብሔር የሚሰግዱለትም በመንፈስና በእውነት ሊሰግዱለት ይገባቸዋል፡፡

2) የአገልግሎት በረከት፡፡

● ኤፌ.4÷15-16

15-ይልቁንም እውነትን በፍቅር እየተናገርን በሁሉም ነገር ራስ ወደ ሆነው ወደ ክርስቶስ እናድጋለን፡፡

16-የተለያዩት የሰውነት ክፍሎች የሚገጣጠሙት በክርስቶስ ነው፤ አካልም በሙሉ የተያያዘው በመገጣጠሚያዎቹ ነው፤ ስለዚህ እያንዳንዱ የአካል ክፍል የተመደበለትን ተግባር በሚገባ ሲያከናውን ያድጋል፤ በፍቅርም ይታነጻል፡፡

3) የህብረት በረከት፡፡ next2

● ሐዋ.2÷46-47

46-እነርሱ በየቀኑ በቤተ መቅደስ በአንድነት ይሰበሰቡ ነበር፤ በቤታቸውም እንጀራ እየቈረሱ በደስታና በጥሩ ልብ ይመገቡ ነበር፤

47-እግዚአብሔርን እያመሰገኑ፣ በሕዝቡ ሁሉ ፊት ሞገስ ነበራቸው፣ ጌታም የሚድኑትን ሰዎች በቍጥራቸው ላይ በየቀኑ ይጨምር ነበር፡፡

4) የዕድገት በረከት፡፡

● ኤፌ.4÷13

13-እንዲሁም የእግዚብሔርን ልጅ በማወቅ በእምነት ወደሚገኘው አንድነት ደርሰን፣ ክርስቶስ ፍጹምና ሙሉ እንደሆነው ዐይነት እኛም ሙሉ ሰው እንድንሆን ነው፡፡

5) **የሕይወት ምስክርነት በረከት፡፡ ኢየሱስ ክርስቶስ ጌታ እንደሆነ ለሰዎች የሚሰብኩ በምድርም በሰማይም** 100 **እጥፍ በረከት እንደሚቀበሉ መጽሐፍ ቅዱስ ይገልጻል፡፡**

- **ማር**.10÷30

30. **በዚህ ዘመን እንኳ ከስደት ጋር ቤቱን፣ ወንድሙን፣ እኅቱን፣ እናቱን፣ ልጆችንና ርስትን በመቶ እጥፍ ይቀበላል፣ በሚመጣውም ዓለም የዘለዓለምን ሕይወት ያገኛል፡፡**

ምዕራፍ 12

12. አንተ አሁን ደስተኛ ነህ? (ሮሜ 3÷23)

● ሮሜ 3÷23

23-ሰዎች ሁሉ ኃጢአት ሠርተዋል፤ እግዚአብሔር የሰጣቸውንም ክብር አጥተዋል፡፡

ማንኛውም ሰው በዚህ ምድር ሲኖር ደስታን ይፈልጋል፡፡ ነገር ግን ብዙ ሰዎች ያንን ፈልጎ ሳያገኙ በመከራ፣ በህመም፣ በቤተሰብ ችግር፣ በጤና ችግር፣ በኢኮኖሚ ችግር፣ ስለወደፊት ኑሮ በማሰብ ችግርና በአዕምሮ ህመም ችግር ይወድቃሉ፡፡ ከዚያም በኋላ ጊዜያዊ ደስታ ሊያገኛሉ ይችላሉ፤ ነገር ግን ዘላቂ የሆነ ደስታን አያገኙም፡፡ ለምን አያገኙም? እነዚህ ሰዎች እግዚአብሔርን ትተው ኃጢአት ስለሚሠሩ ነው፡፡

★ የክፍት ስብሰባ ስራ

① የሰውን ሕይወት የሚነካ ስብሰባ ልንሰብክ ያስፈልጋል፡፡ ኢየሱስ ክርስቶስን የማያምኑ ሙታኖች ናቸው፡፡ ምክንያቱም ሰው ጌታ ኢየሱስ ክርስቶስን እንደ ግል አዳኝ አድርጎ ሲቀበል መንፍስ ቅዱስ በውስጡ ይመጣል፤ ነገር ግን ኢየሱስን የማያምኑ ሰዎች ወደ ሲኦል ይሄዳል፡፡

② ስለ ደህንነት ወንጌል ብዙ ጊዜ መስበክ ያስፈልጋል፡፡ ወንጌል ለሕይወታችን መፍትሄ የሚሰጥ ነው፡፡

③ ስለ ኢየሱስ ክርስቶስ፤ የሰው ሕይወት የሚያንጽ ቃል መስበክ ያስፈልጋል፡፡ ኢየሱስ የሕይወታችን መፍትሄ የሚሰጥ ነው፡፡

④ ኢየሱስ አዳኝና መሲህ እንደሆነ መስበክ ይገባል።

⑤ ስለ ተልዕኮ መስበክ ያስፈልጋል፡፡ ተልዕኮ ከሌለ ክርስቲያኖች እንደ እንስሳ ናቸው፡፡ እኛ ወደ ሁሉም አገር ሄደን ደቀመዝሙር ልናደርግ ይገባል።

ስብሰባ፤

መልካም ሰውን የሚያይ ዐይን ሊኖረን ይገባል፡፡

እግዚአብሔርን የሚፈልግ ሰው፡- ለምሳሌ ለዛሬና ለወደፊት የተዘጋጀ ሰው

አምሮ የካደውን ሰው፣ የወንጌል ምስጢር ያላወቀውን ሰው፣ ዳግመኛ ያልተወለደውን የሚያይ

የተልዕኮ ሰው(ወንጌልን ሰምተው እንደ ቃሉ የሚታዘዝ ሰው)

ታማኝ የሆነ ሰው፤ የእግዚአብሔርን ቃል የሚታዘዝ ሰው፤ ደቀመዝሙር ለማድረግ በኮሌጅ ለመሥራት ብቁ የሆነውን ሰው የሚያይ ሰው ያስፈልጋል፡፡ ብዙ ደቀመዝሙር እንዲሆኑ ብቻ ሳይሆን ቀጣይነት ያለውን ሥራ እንዲሠሩ ነው፡፡

1. ሰው እግዚአብሔርን ትተው ኃጢአት ሠርተው ከወደቀ በኃላ ምን እንደሚሰራ ተናገር፡፡

1) እግዚአብሔር ሰውን እንደ ራሱ ምስል አድርጎ ሲፈጥር እንዲደሰቱና በሕይወት እንዲኖሩ ሁሉንም ነገር ሰጠ፡፡

- ዘፍ.1÷27-28

27-በዚህ ዐይነት እግዚአብሔር ሰውን በራሱ መልክ ፈጠረ፤ ወንድና ሴት አድርጎም ፈጠራቸው፡፡

28-እግዚአብሔርም “ብዙ፣ ተባዙ፣ ዘራችሁ ምድርን ይሙላ፤ ምድርም በቊጥጥራችሁ ሥር ትሁን፤ በባሕር ውስጥ በሚኖሩ ዓሣዎች፣ በሰማይ በሚበርሩ ወፎችና በምድር ላይ በሚንቀሳቀሱ ሕያዋን ፍጥረቶች ሁሉ ላይ ሥልጣን ይኑራችሁ” ብሎ ባረካቸው፡፡

2) ነገር ግን ሰው ኃጢአት ከሰራ በኃላ እግዚአብሔርን ተወው

- ዘፍ.3÷1-5

1-እግዚአብሔር አምላክ ከፈጠራቸው አራዊት ሁሉ፣ እባብ እጅግ ተንኰለኛ ነበረ፤ ስለዚህ እባብ “በአትክልቱ ቦታ ካሉት ዛፎች ሁሉ ፍሬ እንዳትበሉ በእርግጥ እግዚአብሔር አዞአችኋልን?” ሲል ሴቲቱን ጠየቃት፡፡

2-ሴቲቱም “በአትክልት ቦታ ካሉት ዛፎች ፍሬ ልንበላ እንችላለን፤

3-ነገር ግን እግዚአብሔር ‘በአትክልቱ ቦታ ካለው ዛፍ ፍሬ አትብሉ፤ በእጃችሁም አትንኩት፤ ይህን ብታደርጉ ትሞታላችሁ’ ብሎ አስጠንቅቆናል” ስትል መለሰችለት፡፡

4-እባቡም እንዲህ አላት፡- “በፍጹም አትሞቱም፤

5-እግዚአብሔር ይህን ያዘዛችሁ ከዚያ ዛፍ ፍሬ በበላችሁ ጊዜ እንደ እግዚአብሔር እንደምትሆኑና ደጉን ከክፉ ለይታችሁ እንደምታውቁ ስለሚያውቅ ነው፤”

3) የእግዚአብሔርን ክብር ማጣት

● ሮሜ.3÷23

23. ሰዎች ሁሉ ኃጢአት ሠርተዋል፤ እግዚአብሔር የሰጣቸውንም ክብር አጥተዋል፡፡

4) በሰው ሕይወት ላይ ችግሮችና ህመሞች ቀጠሉ፡፡

ወንድ በድካሙ ምግብ እንደምበላና ሴት እንደምትወልድ መከራ መጣ

● ዘፍ.3÷16-19

16-ሴቲቱንም፣ “በእርግዝናሽ ወራት ጭንቀትሽን፣ በምትወልጂበትም ጊዜ የምጥ ሥቃይሽን አበዛሁ፤ ይህም ሁሉ ሆኖ ፍላጎትሽ ለባልሽ ይሆናል፡፡ ለእርሱም ታዛዥ ትሆኚአለሽ” አላት፡፡

17-አዳምንም እንዲህ አለው፣ “የሚስትህን ቃል ሰምተህ ‘አትብላ’ ያልኩህን ፍሬ ከዛፉ ወስደህ ስለ በላህ፣ አንተ በፈጸምከው ክፉ ሥራ ምክንያት ምድር የተረገመች ትሁን፤ በሕይወት ዘመንህ ሁሉ ምግብህን ከእርስዋ የምትበላው በብርቱ ድካም ነው፡፡

18-ምድር እሾኽና አሜከላ ታበቅላለች፤ አንተም የዱር ተክሎችን ትበላለህ፡፡

19-ወደ መጣህበት ወደ መሬት እስክትመለስ ድረስ፣ እንጀራህን ትበላለህ፡፡” ዐፈር ነህና፣ ወደ ዐፈርም ትመለሳለህ፡፡

2. ሰው እግዚአብሔርን ሲተው በህመምና በሀዘን ይኖራል

1) እውነተኛ ሰላምና ዕረፍት ስለሌለ

● ዮሐ.10÷10

10. ሌባው ሊሰርቅ፣ ሊገድልና ሊያጠፋ ብቻ ይመጣል፣ እኔ የመጣሁት በጎቼ ሕይወት እንዲያገኙና የተትረፈረፈ ሕይወት እንዲኖራቸው ነው፡፡

2) በባዶነትና በትርጉም አልባ ሕይወት ስለሚኖር

● ማቴ.11÷28

28. እናንተ ደከሞች ሸክማችሁ የከበደ ሁሉ ወደ እኔ ኑ፣ እኔም አሳርፋችኋለሁ፡፡

3) የአዕምሮ ህመምተኛና የስጋ ደዌ ህመምተኛ በመሆን ይኖራል፡፡

● ማቴ.9÷36

36. ኢየሱስም ሕዝብን ባየ ጊዜ አዘነላቸው፥ እነርሱ እረኛ እንደ ሌላቸው በጎች ተጨንቀው ተጥለውም ነበርና።

4) በተረገመ አካባቢ ይኖራል፡፡ ይህ ማለት መከራና አደጋ ገንዘብ ማጣት ይከሰታል ማለት ነው፡፡

● ማቴ.8÷1-18

1. ኢየሱስም ከተራራ በወረደ ጊዜ፣ ብዙ ሕዝብ ተከተሉት።

2. በዚህ ጊዜ፣ አንድ ለምጻም ሰው ወደ ኢየሱስ መጥቶ ሰገደለት እንዲህም አለው። “ጌታ ሆይ፥ ብትፈቅድስ ልታነጻኝ ትችላለህ”

3. ኢየሱስም እጁን ዘርግቶ ለምጻሙን ዳሰሰውና፣ “እኔ ያንተን መዳን እፈልጋለሁ፣ ንጻ!” አለው፡፡ ወዲያውም ለምጹ ነጻ።

4. ከዚህ በኋላ ኢየሱስ እንዲህ አለው። “ለማንም ይህን አትናገር፣ ነገር ግን ብቻ ሄደህ መዳንህን ለካህን አሳይ፥ ሙሴ ያዘዘውን መባ ለእግዚአብሔር አቅርብ፣ ለእነርሱም ይህ ምስክር ይሆንላቸዋል።

5. ኢየሱስም ወደ ቅፍርናሆም ከተማ በገባ ጊዜ፣ አንደ ሮማዊ የመቶ አለቃ ወደ እርሱ ቀርቦ ለመነው።

6. ሮማዊ የመቶ አለቃም እንዲህ አለው። “ጌታ ሆይ፥ አገልጋዬ በቤቴ ሽባ ሆኖ ተኝቶአል፣ እጅግም እየተሣቀየ ነው።

7. ኢየሱስም እንዲህ አለው። “እኔ መጥቼ እፈውሰዋለሁ”

8. የመቶ አለቃው መለሰ እንዲህ አለው። “ጌታ ሆይ፥ አንተን ወደ ቤቴ እንድትገባ እኔ የተገባሁ ሰው አይደለሁም፣ ነገረ ግን አንዲት ቃል ብቻ ተናገር፣ አገልጋዬም ይፈወሳል።

9. እኔ ራሴ ለሌላ ተገዥ ነኝና፥ ከእኔም በታች ጭፍራ አለኝ፤ እኔ ባሪያዬን “ሂድ!” ብለው ይሄዳል፥ “ና!” ብለው ይመጣል፥ ባሪያዬንም “ይህን አድርግ!” ብለው

ያደርጋል።

10. ኢየሱስም ይህን ቃል ሰምቶ ተደነቀና ለተከተሉት እንዲህ አላቸው፣ “እኔ እውነት እላችኋለሁ፥ እኔ እስካሁን ድረስ በእስራኤል እንኳ እንዲህ ያለ ትልቅ እምነት ያለው አንድ ሰው አላገኘሁም”

11. እኔ እላችኋለሁም፥ “ብዙዎች ከምሥራቅና ከምዕራብ ይመጣሉ፣ በመንግሥተ ሰማይ ከአብርሃምና ከይስሐቅ ከያዕቆብም ጋር ይቀመጣሉ ይበላሉ፡፡

12. ነገር ግን የአይሁድ ልጆች ወደ ውጭ ወደ ጨለማም ይጣላሉ፤ በዚያም ለቅሶና ጥርስ ማፋጨት ይሆናል”

13. ከዚህ በኋላ፣ ኢየሱስ ለመቶ አለቃ እንዲህ አለው። “ሂድ፣ እንደ እምነትህ ይሁንልህ!” አገልጋዩም በዚያች ሰዓት ተፈወሰ።

14. ኢየሱስም ወደ ጴጥሮስ ቤት በገባ ጊዜ የጴጥሮስ አማቱ በትኵሳት ታማ ተኝታ አያት፡፡

15. ኢየሱስም እጅዋን በዳሰሳት ጊዜ፣ ትኩሳቱም ለቀቃትና ዳነች፣ እርሱዋም ተነሥታ ኢየሱስን አገለገለችው።

16. በመሽም ጊዜ ሰዎች በአጋንንት የተያዙ ብዙ በሽተኞችን ወደ ኢየሱስ አመጡ፣ ኢየሱስም በቃሉ መናፍስትን አስወጣ፣ በሽተኞችንም ሁሉ ፈወሰ፡፡

17. ይህ በነቢዩ ኢሳይያስ እንዲህ ብሎ የተናገረው ትንቢት ተፈጸመ፣ “እርሱ ሕመማችንን ተቀበለ፣ ደዌያችንንም ተሸከመ”

18. ኢየሱስም ብዙ ሰዎች በዙሪያው ተሰብስበው ባየ ጊዜ ለደቀመዛሙሮች ወደ ባሕሩ ማዶ እንዲሻገሩ አዘዛቸው።

5) በሞት ፍርሃት ውስጥ ይኖራል

● ዕብ.9÷27

27-ለሰው አንድ ጊዜ መሞት ተመድቦለታል፤ ከሞት በኋላም ፍርድ አለበት፡፡

6) የዚህ ሁሉ ምክንያት መንፈሳዊውን ነገር አላማወቀ ነው፡፡

● ኤፌ.3÷1

1-ስለዚህ እኔ የጳውሎስ የኢየሱስ ክርስቶስ እስረኛ የሆንኩ ለእናንተ ለአሕዛብ ስል ነው፡፡

3. እግዚአብሔርን የሚተው ሰዎች ለህመማቸውና ለስቃያቸው መፍትሄ የሚሰጥ ጠንቃይና ሌሎችን ጣኦታት ይፈልጋሉ

የዚህ ነገር ውጤት ምንድን ነው?

1) ሠርቶ ጥቅም አልባ ይሆናሉ፡፡

- ማቴ.12÷43-44

43. ቀጥሎም ኢየሱስ እንዲህ አለ፣ “ርኩስ መንፈስ ከሰው በወጣ ጊዜ የሚያርፍበት ቦታ በመፈለገ ውሃ በሌለበት በደረቅ ቦታ ይዞራል፡፡ ነገር ግን አያገኝም፣

44. ርኩስ መንፈስ እንዲህ አለ፡፡ ‘እኔ ወደ ወጣሁበት ቤት ተመልሼ ልሂድ’ ይላል፣ ወደ ቤቱ ተመልሶ ሲመጣ፣ ቤቱ ባዶ ሆኖ፣ ጸድቶ፣ ተዘጋጅቶ ያገኘዋል፡፡

2) ለራሳቸው መፍተሄ ያጣሉ፡፡

- ማቴ. 12÷28-29

28. ነገር ግን እኔ በእግዚአብሔር መንፈስ አጋንንትን የማስወጣ ከሆነ፣ እንግዲህ የእግዚአብሔር መንግሥት በእናንተ ላይ መጥታለች ማለት ነው፡፡

29. ደግምስ አንድ ሰው አስቀድሞ ኃይለኛውን ሳያስር ወደ ኃይለኛው ቤት ገብቶ ንብረቱን መዝረፍ እንዴት ይችላል? ኃይለኛውን ካሰረው በኋላ ቤቱን መበዝበዝ ይችላል፡፡

3) በሃይማኖታቸው ደስተኞ አይሆኑም፡፡

- ማቴ.11÷28

28. እናንተ ደከሞች ሸክማችሁ የከበደ ሁሉ ወደ እኔ ኑ፣ እኔም እኔም አሳርፋችኋለሁ፡፡

4) ተጨማሪ ህመም በራሳቸው ላይ ይጨምራሉ፡፡ ሰይጣንን ማገልገል ህመም መጨመር እንጂ ሌላ ትርፍ የለም፡፡

- ማቴ.12÷45 45. ከዚህ በኋላ፣ ርኩሱ መንፈስ ይሄድና ከእርሱ ይብሰ የከፋትን ሌሎች ሰባት አጋንንት ይዞ ይመጣል፡፡ እነርሱም ሰውየው ውስጥ ገብተው ይኖራሉ፡፡

የዚያም ሰው የኋለኛው ሁኔታ ከፊተኛው የከፋ ይሆናል፡፡ በዚህ ክፉ ትውልድም ላይ እንዲሁ ይሆንበታል፡፡”

5) እግዚአብሔርን እስካላገኙ ድረስ እውነተኛ ደስታ የላቸውም፡፡

● ኢሳይያስ. 44÷3-4

3-በተጠማ ላይ ውኃን በደረቅም መሬት ላይ ፈሳሾችን አፈስሳለሁና መንፈሴን በዘርህ ላይ በረከቴንም በልጆችህ ላይ አፈስሳለሁ፥

4-በፈሳሾችም አጠገብ እንደሚበቅሉ እንደ አኻያ ዛፎች በሣር መካከል ይበቅላሉ።

4. ኢየሱስ ክርስቶስ ብቻ መፍትሄ ይሰጣል፡፡ ለዚህ ምክንያቱ ምንድን ነው?

1) ኢየሱስ ከእግዚአብሔር ጋር የሚያገናኝ እውነተኛ መንገድ ነው፡፡

● ዮሐ.14÷6

6. ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰለት፣ “እኔ መንገድና እውነት ሕይወትም ነኝ፤ በእኔ በኩል ካልሆነ በቀር ማንም ወደ አብ የሚመጣ የለም፡፡

2) ከችግሮች ሁሉ ነፃ የሚያወጣ ስለሆነ ለችግሮችን ሁሉ መፍትሔ ይሰጣል

● ሐዋ.10÷38

38-እግዚአብሔር የናዝሬቱን ኢየሱስ በመንፈስ ቅዱስና በኀይል ቀባው፤ ኢየሱስ መልካም ነገርን እያደረገ በዲያብሎስ የተያዙትን ሁሉ ፈወሰ፤ እግዚአብሔርም ከኢየሱስ ጋር ነበረ፡፡

3) ኢየሱስ ወደ እኛ የመጣበት ዋና ምክንያት የተትረፈረፈ ሕይወትንና ደስታን ለመስጠት ነው፡፡

● ዮሐ.10÷10

10. ሌባው ሊሰርቅ፣ ሊገድልና ሊያጠፋ ብቻ ይመጣል፣ እኔ የመጣሁት በጎቼ ሕይወት እንዲያገኙና የተትረፈረፈ ሕይወት እንዲኖራቸው ነው፡፡

4) ኢየሱስ ክርስቶስን እንደ ግል አዳኝና ጌታ አድርገን በልባችን እንቀበለዋለን።

● ዮሐ.1÷12-13

12. *ነገር ግን ኢየሱስ ራሱ ለተቀበሉትና በስሙ ላመኑት ሰዎች ሁሉ የእግዚአብሔር ልጆች የመሆን መብት ሰጣቸው፡፡*

13. *እነርሱም ከእግዚአብሔር ተወለዱ እንጂ ከደም ወይም ከሥጋ ፈቃድ ወይም ከሰው ፈቃድ አልተወለዱም።*

*ምሳሌ - የሕይወታችን የመጀመሪያ ሹፌር ሊናደርገው ያስፈልጋል፡፡ ወደ ሕይወት ስለሚወስደው መንገድ በመጀመሪያ መጨነቅ አለብን፡፡ሕይወታችንን በኢየሱስ እጅ አሳልፈን ከሰጠን እርሱ የእኛ ሹፌር ይሆናል፤ ሰላማችንና መሪያችን ይሆናል፡፡*

5) *አሁን አንተ ዛሬን ለክብሩ ለመኖር ወሳን።*

● *ምሳሌ* 27፡1 1-*ቀን የሚያመጣውን ምን እንደ ሆነ አታውቅምና ነገ በሚሆነው አትመካ።*

5. *ኢየሱስ ክርስቶስን ከተቀበልህ በኃላ ልዩ ስልጣን ምንድን ነው*?

1) *የእግዚአብሔር ልጅ መሆን፡፡*

*አሁን እኛ የእግዚአብሔር ልጆች ነን፡፡*

● ዮሐ.1÷12

12. *ነገር ግን ኢየሱስ ራሱ ለተቀበሉትና በስሙ ላመኑት ሰዎች ሁሉ የእግዚአብሔር ልጆች የመሆንን መብት ሰጣቸው፡፡*

2) *ኃጢአታችንና እርግማናችን ወዲያውኑ ተወግዶአል ፤ የመጀመሪያው ኃጢአት፣የአሁኑና የወደፊቱ ሁሉም ተወግደዋል፡፡*

● ሮሜ.8÷2

2. በክርስቶስ ኢየሱስ የሚገኘውን ሕይወት የሚሰጥ የመንፈስ ቅዱስ ሕግ ከኃጢአትና ከሞት ሕግ ነጻ አውጥቶኛል፡፡

3) ስንፀልይ ምላሽ እንቀበላለን፡፡

ከአሁን ጀምሮ በኢየሱስ ስም ብንፀልይ እግዚአብሔር ምላሽ ይሰጣል፡፡

● ዮሐ.16÷24

24. እስከ አሁን እናንተ በስሜ ምንም ነገር አለመናችሁም፣ ለምኑ ይሰጣችኋል፣ ደስታችሁም ፍጹም ይሆናል፡፡

4) ኢየሱስ ክርስቶስን በማመናችን ሰላም፣ ደስታና ዕረፍት ይበዛልናል፡፡

● ማቴ.11÷28

28. እናንተ ደከሞች ሸክማችሁ የከበደ ሁሉ ወደ እኔ ኑ፣ እኔም እኔም አሳርፋችኋለሁ፡፡

5) የኢየሱስ የስሙ ሥልጣን በየቀኑ አሸናፊዎች ያደርገናል፡፡

● ሐዋ.3÷6-8

6-ጴጥሮስ ግን፣ “እኔ ብርና ወርቅ የለኝም፤ ነገር ግን ያለኝን እሰጥሃለሁ፤ በናዝሬቱ በኢየሱስ ክርስቶስ ስም ተነሥተህ በእግርህ ተመላለስ” አለው፤

7-ቀኝ እጁንም ይዞ አስነሣው፤ ወዲያውኑ እግሩና ቍርጭምጭሚቱ በረታ፡፡

8-ዘሎም ቀጥ ብሎ ቆመ፤ እየተራመደም ከእነርሱ ጋር ወደ ቤተ መቅደስ ገባ፤ እየተራመደና እየዘለለም እግዚብሔርን ያመሰግን ነበር፡፡

አስታውክ - በክፍት ስብሰባ በየሳምንቱ በተመሳሳይ ስፍራና በተመሳሳይ ሰዓት አንድ ላይ በመሆን መማማርና መስበክ መልካም ነው፡፡

ምዕራፍ 13

13. አንተ አሁን ማታመን ያስፈልጋል ነው (ሐዋ.4÷12)

● ሐዋ.4÷12

12-መዳን ከኢየሱስ በቀር በሌላ በማንም የለም፤ እግዚብሔር ከሰማይ በታች እኛ ልንድንበት የሚገባን ሌላ ስም ለሰዎች የተሰጠ ስም የለም፡፡

ዓሣ ከውሃ ወጥሮ መኖር እንደማይችል እንደዚሁም ዛፍ ከምድር በላይ መኖር እንደማይችል ሁሉ ሰውም ከእግዚአብሔር ተለይቶ መኖር አይችልም፡፡ ሰው ሀዘንተኛ ሆኖ የመኖሩ ምክንያት እግዚአብሔርን ስለተወው ነው፡፡ እግዚአብሔር የሌለበት ቤተሰብ፣ ማህበረሰብ፣መላው አለም በእርግማንና በ¸ጢአት ውስጥ ለቀጣይነት ይኖራል፡፡ አሁን ሰው ወደ እግዚአብሔር ቢመለስ እግዚአብሔር በሕይወቱ ደስታን ይጨምራል፤ እግዚአብሔር አሁን እኛ ወደ እርሱ እንድንመለስ ፈልጎ ይታገሳል፡፡

1. እግዚአብሔርን የተወው ሰው ምን አይነት ቅርፅ አለው?

1) በመጀመሪያ ሰው ከእግዚአብሔር መንፈስ ጋር ይኖራል፡፡

● ዘፍ.1÷27

27-በዚህ ዐይነት እግዚአብሔር ሰውን በራሱ መልክ ፈጠረ፤ በእግዚአብሔር መልክ ፈጠረው፤ ወንድና ሴት አድርጎም ፈጠራቸው፡፡

2) ኃጢአት ስሠራ የእግዚአብሔር መንፈስ ከእርሱ ይለያል፤ ከዚያም ያ ሰው የሞተ ነው፡፡

● ኤፌ.2÷1

1-እናንተ በበደላችሁና በኃጢአታችሁ ምክንያት በመንፈሳዊ ኑሮአችሁ የሞታችሁ ነበራችሁ፤

3) ውጤቱም በክፉ መንፈስ በአጋንንት ይመራል፡፡

● 1ቆሮ.2÷12

12-ከእግዚአብሔር የተሰጠንን ነገር እንድናውቅ የእግዚአብሔርን መንፈስ እንጂ የዚህን ዓለም መንፈስ አልተቀበልንም፡፡

4) የሰይጣንን ምሪት የተቀበለ ሰው በሥጋዊ ቀውስና በመንፈሳዊ ውድቀት ውስጥ ይኖራል።

- ዘፍ.3÷16-19

16-ሴቲቱንም፣ "በእርግዝናሽ ወራት ጭንቀትሽን፣ በምትወልጂበትም ጊዜ የምጥ ሥቃይሽን አበዛሁ፤ ይህም ሁሉ ሆኖ ፍላጎትሽ ለባልሽ ይሆናል፡፡ ለእርሱም ታዛዥ ትሆኚአለሽ" አላት፡፡

17-አዳምንም እንዲህ አለው፣ "የሚስትህን ቃል ሰምተህ 'አትብላ' ያልኩህን ፍሬ ከዛፉ ወስደህ ስለ በላህ፣ አንተ በፈጸምከው ክፉ ሥራ ምክንያት ምድር የተረገመች ትሁን፤ በሕይወት ዘመንህ ሁሉ ምግብህን ከእርስዋ የምትበላው በብርቱ ድካም ነው፡፡

18-ምድር እሾኽና አሜከላ ታበቅላለች፤ አንተም የዱር ተክሎችን ትበላለህ፡፡

19-ወደ መጣህበት ወደ መሬት እስክትመለስ ድረስ፣ እንጀራህን በግንባርህ ላብ ትበላለህ፡፡" ዐፈር ነህና፣ ወደ ዐፈርም ትመለሳለህ፡፡

5) ከሞት በኃላ ፍርድ ተቀብሎ ወደ ዘላለም ሲኦል ይወርዳል፡፡

- ራዕ.21÷8

8-ነገር ግን ፈሪዎች፣ እመነት ቢሶች፣ ርኩሶች፣ ነፍሰ ገዳዮች፣ አመንዝሮች፣ አስማተኞች፣ ጣዖት አምላኪዎች ውሸታሞች ሁሉ ዕጣ ክፍላቸው በዲን በሚቃጠለው በእሳት ባሕር ውስጥ ይሆናል፤ ይህ ሁለተኛው ሞት ነው፡፡"

6) የመንፈሳዊ ቀውስ ከ3ኛ-4ኛ ትውልድ ድረስ የተረገመ ይሆናል::

ጣኦትና ጠቋንይ የሚያምኑ ሰዎች ከሰይጣን ጋር ይኖራሉ፡፡ኃጢአትና ህመም ከ3ኛ-4ኛ ትውልድ ድረስ የተረገሙ ይሆናሉ፡፡

- ዘፀ.20÷4-5

4-በ"ሰማይም ሆነ በምድር ወይም ከምድር በታች ባለው ውሃ ውስጥ ከሚኖሩት ነገሮች የማንኛውንም ዐይነት ምስል ጣዖት አድርገህ አትሥራ፤

5-እኔ እግዚአብሔር አምላክህ እጅግ ቀናተኛ ስለ ሆንኩ ተቀርጾ የተሠራውን ማንኛውም ጣዖት አታምልክ፤ አትስገድለትም፤ እኔ የሚጠሉኝን ሁሉ እቀጣለሁ፤ ዘራቸውንም ሁሉ እስከ ሦስትና አራት ትውልድ ድረስ እበቀላለሁ፡፡

2. ሰው ራሱን ሳያውቅ እግዚአብሔርን ይፈልጋል፡፡

1) ሰው መንፈስ ስላለው እግዚአብሔርን ይፈልጋል፡፡

● ሮሜ.1÷18-20

18. ሰዎች በክፋታቸው እውነት እንዳይታወቅ ያደርጋሉ፤ እግዚአብሔርንም ባለመፍራታቸውና በክፋታቸው ምክንያት በሁሉም ላይ የእግዚአብሔር ቊጣ ከሰማይ ይገለጣል፡፡

19. ስለ እግዚአብሔር ሊታወቅ የሚቻለው ለእነርሱ ግልጽ ነው፤ ምክንያቱም እግዚአብሔር ለእነርሱ ግልጽ አድርጎታል፡፡

20. ዓለም ከተፈጠረ ጀምሮ የማይታየው የእግዚአብሔር ባሕርይ ይኸውም ዘላለማዊ ኀይሉና መለኮትነቱ፣ ከፍጥረቱ በግልጽ ይታያል፤ ስለዚህ ሰዎች ማመካኛ የላቸውም፡፡

2) ሰው በማመን ከእግዚአብሔር ጋር ስገናኝ፤ በእምነቱ እንድፀና ያደርጋል፡፡

● ማቴ.12÷43-45

43. ቀጥሎም ኢየሱስ እንዲህ አለ፣ “ርኩስ መንፈስ ከሰው በወጣ ጊዜ የሚያርፍበት ቦታ በመፈለግ ውሃ በሌለበት በደረቅ ቦታ ይዞራል፡፡ ነገር ግን አያገኝም፣

44. ርኩስ መንፈስ እንዲህ አለ፡፡ ‘እኔ ወደ ወጣሁበት ቤት ተመልሼ ልሂድ’ ይላል፣ ወደ ቤቱ ተመልሶ ሲመጣ፣ ቤቱ ባዶ ሆኖ፣ ጸድቶ፣ ተዘጋጅቶ ያገኘዋል፡፡

45. ከዚህ በኋላ፣ ርኩሱ መንፈስ ይሄድና ከእርሱ ይባሰ የከፋትን ሌሎች ሰባት አጋንንት ይዞ ይመጣል፡፡ እነርሱም ሰውየው ውስጥ ገብተው ይኖራሉ፡፡ የዚያ ሰው የኋለኛው ሁኔታ ከፊተኛው ይልቅ የከፋ ይሆናል፡፡ በዚህ ክፋ ትውልድም ላይ እንዲሁ ይሆንበታል፡፡”

3) በመልካም ሥራና በፍልስፍና ከእግዚአብሔር ለመገናኘት መሞከር ውድቀትን ያመጣል፡፡

● ቆላ.2÷8-9

8-በክርስቶስ ላይ የተመሠረተ ሳይሆን በሰው ሠራሽ ወግና በዓለማዊ ተራ ሥርዓት ላይ በተመሠረተ በልሰፍናና በከንቱ ሽንገላ ማንም እንዳያጠምዳችሁ ተጠንቀቁ፡፡

9-የአምላክነት ፍጹም ሙላት በአካል ተገልጦ የሚኖረው በክርስቶስ ነው፡፡

4) ያለ እግዚአብሔር ንብረትንና ስልጣንን መመኘት ከንቱ ያደርጋል፡፡ እንዲሁም ባዶነትን ያስከትሳል።

● 1ዮሐ.2÷16

16-በዓለም ያለው ሁሉ የሥጋ ምኞት፣ የዐይን አምሮት፣ የኑሮ ትምክሕት ከዓለም ነው እንጂ ከእግዚአብሔር አብ አይደለም፡፡

3. አንተ አሁን በሰይጣን አትታለል።

1) ሰው ድህንነትን ሳይቀበል እግዚአብሔርን መገናኘት አይችልም፡፡

● ሐዋ.4÷12

12-መዳን ከኢየሱስ በቀር በሌላ በማንም የለም፤ እግዚብሔር ከሰማይ በታች እኛ ልንድንበት የሚገባን ሌላ ስም ለሰዎች የተሰጠ ስም የለም፡፡

2) ዳግም ሳይወለዱ እግዚአብሔርን ማየት አይቻልም፡፡

● ዮሐ.3÷3-5

3. ኢየሱስም መልሶ እንዲህ አለው፡፡ “እኔ እውነት እውነት እልሃለሁ፣ ሰው ዳግመኛ ካልተወለደ በቀር የእግዚአብሔርን መንግሥት ሊያይ አይችልም”

4. ኒቆዲሞስም ለኢየሱስ እንዲህ አለው፡፡ “ታዲያ፣ ሰው ከሸመገለ በኋላ እንዴት ሊወለድ ይችላል? ዳግመኛ ወደ እናቱ ማሕፀን ገብቶ መወለድ ይችላል?”

5. ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰ፣ “እኔ እውነት እውነት እልሃለሁ፣ ማንም ከውሃና ከመንፈስ ቅዱስ ካልተወለደ በቀር ወደ እግዚአብሔር መንግሥት ሊገባ አይችልም፡፡

3) ማዳን ማለት ሁሉ ኃጢያት ካበላሸው ሕይወት መውጣት ማለት ነው፡፡

a. የአዳም ኃጢያት ካበላሸው

● ሮሜ.5÷19

19. በአዳም አለመታዘዝ ምክንያት ብዙዎች ኃጢአተኞች እንደ ሆኑ እንዲሁም በክርስቶስ መታዘዝ ምክንያት ብዙዎች ይጸድቃሉ፡፡

b. ከእንደገና ኃጢአት ማለትም ራሱ የሠራው ኃጢአት ካበላሸበት

● ገላ.5÷19-21

19-የሥጋ ሥራዎች የታወቁ ናቸው፤ እነርሱም ዝሙት፣ ርኩሰት፣ ስድነት፤

20-ጣዖትን ማምለክ፣ ሟርት፣ ጠላትነት፣ ንትርክ፣ ቅናት፣ ቊጣ፣ ራስ ወዳድነት፣ መለያየት፣ አድመኛነት፣

21-ምቀኝነት፣ ስካር፣ ቅጥ ያጣ ፈንጠዝያ እነዚህን የመሳሰሉ ናቸው፤ ከዚህ በፊት እንዳስጠነቀቅኳችሁ አሁንም በድጋሚ አስጠነቅቃችኋለሁ፤ እንደ እነዚህ ያሉትን ነገሮች የሚያደርጉ ሰዎች የእግዚአብሔርን መንግሥት አይወርሱም፡፡

c. የአያቶቻቸው ኃጢአት ካለባቸው

● ዘፀ.20÷4-5

4-በ"ሰማይም ሆነ በምድር ወይም ከምድር በታች ባለው ውሃ ውስጥ ከሚኖሩት ነገሮች የማንኛውንም ዐይነት ምስል ጣዖት አድርገህ አትሥራ፤

5-እኔ እግዚአብሔር አምላክህ እጅግ ቀናተኛ ስለ ሆንኩ ተቀርጾ የተሠራውን ማንኛውም ጣዖት አታምለክ፤ አትስገድለትም፤ እኔ የሚጠሉኝን ሁሉ እቀጣለሁ፤ ዘራቸውንም ሁሉ እስከ ሦስትና አራት ትውልድ ድረስ እበቀላለሁ፡፡

ኢየሱስን በማመን ከአዳም ኃጢያት፡ እኛ ከአያቶቻቸው ኃጢአት ሁሉ ይቅርታ ይቀበላል።

4) መዳን ማለት ከሰይጣን ስልጣንና ከጠንቋይ እምነት ነፃ መውጣት ማለት ነው፡፡

● ኤፌ.2÷2

2-በዚያን ጊዜ የዚህን ዓለም ክፉ አካሄድ ትከተሉ ነበር፤ እንዲሁም በአየር ላይ ያሉትን የመናፍስት ኀይሎች ለሚገዛው ትታዘዙ ነበር፤ እርሱ በማይታዘዙት ሰዎች ላይ የሚሠራ ርኩሱ መንፈስ ነው፡፡

● ሮሜ. 8÷2

2. በክርስቶስ ኢየሱስ የሚገኘውን ሕይወት የሚሰጥ የመንፈስ ቅዱስ ሕግ ከኃጢአትና ከሞት ሕግ ነጻ አውጥቶኛል፡፡

5) መዳን ማለት የእግዚአብሔር ልጅ ሆኖ በምድር ብዙ ህይወት እየኖረ ወደፊት በመንግስተ ሰማይ ዙፋን መቀመኘ ማለት ነው፡፡ እንዲሁም የአብርሃም በረከቶችን መቀበል ማለት ነው፡፡

● ኤፌ.2÷6

6-እግዚአብሔር በክርስቶስ ኢየሱስ አማካይነት ከእርሱ ጋር ከሞት አስነሥቶ በሰማያዊው ስፍራ ከእርሱ ጋር አስቀመጠን፡፡

የአብርሃም በረከት ይቀበላል።

● ገላትያ.3÷13-14

13 -14-ይህም የሆነው እግዚአብሔር ለአብርሃም የሰጠው በረከት በኢየሱስ ክርስቶስ አማካይነት ለአሕዛብ እንዲደርስና እኛም እግዚአብሔር እሰጣችኋለሁ ያለውን መንፈስ ቅዱስን በእምነት እንድንቀበል ነው፡፡

6) መዳንን አሁን የተቀበልክ እንደ ሆነ አንተም ምስክርነት ስትናገር እስከ ልጅ ልጅ ድረስ በረከት ትቀበላለህ፡፡

● ኤፌ.2÷7

7-ይህንንም ያደረገው በኢየሱስ ክርስቶስ ለእኛ የገለጠውን ቸርነትና ወደር የሌለውን የጸጋውን ብልጽግና በሚመጡት ዘመናት ሊያሳየን ብሎ ነው፡፡

ኢየሱስን ያመነ ሰው እስከ 1,000 ትውልድ ድረስ በረከትን ይቀበላል፡፡

● ዘፀ.20÷6

6-ለሚወዱኝና ትእዛዞቼን ለሚጠብቁ ሁሉ ግን እስከ ሺህ ትውልድ ድረስ ዘለዓለማዊ ፍቅሬን አሳያቸዋለሁ፡፡

4. በእንዴት ዓይነት ሁኔታ ደህንነትህን ተቀበልህ? በሰው ሙከራ ደህንነትን መቀበል አይቻልም፡፡

1) እግዚአብሔርን ሰው ስተው የሞተ መንፈስ ስላለው ለመዳን ሲሞክር ምንም ሊድን አይችልም፡፡

2) ኢየሱስን ሳያምን ሰው መልካም ሥራ የሚሠራ ከሆነ በውጫዊ ማንነቱ ሊቀየር ይችላል፡፡ ነገር ግን ኢየሱስን ያመነ ውስጣዊ ማንነቱ ይቀይራል፡፡

3) ሰው ኃጢአትንና ሰይጣንን ከቶ አያሸንፍም፡፡ ነገር ግን ኢየሱስ ክርስቶስን ያመኑ ክርስቲያኖች ኃጢአትንና ሰይጣንን አሸነፍ፡፡ ምክንቱም ኢየሱስ ለእነርሱ ድልን ስለሰጠ ነው፡፡

4) ደህንነት ከእግዚአብሔር የሚሰጥ ስጦታ ነው፡፡

● ኤፌ.2÷8-9

8-እናንተ የዳናችሁት በእምነት አማካይነት በጸጋው ነው፤ ይህም የእግዚአብሔር ስጦታ ነው እንጂ በእናንተ ሥራ የተገኘ አይደለም፡፡

9-ማንም ሰው እንዳይመካ፣ የመዳን ጸጋ የተገኘው በሥራ አይደለም፤

5. እግዚአብሔር ለእኛ የደህንነትን መንገድ አዘጋጀ፡፡

1) ኢየሱስ ሰውን ለማዳን የሰው አካል ለብሶ ወደዚህ ምድር መጣ፡፡

● ዮሐ.1÷14

14. ቃልም ሥጋ ሆነ፣ በመካከላችንም ኖረ፣ እኛም ጸጋንና እውነትን ተሞልቶ ከአባቱ ዘንድ የመጣውን የአንድያ ልጁን ክብር አየን፡፡

2) የሰውን ሥጋ የለበሰው ኢየሱስ ክርስቶስ ነው፡፡

● ማቴ.1÷21

21-ማርያም ወንድ ልጅ ትወልዳለች፤ ስሙንም ኢየሱስ ብለህ ትጠራዋለህ፣ እርሱ ሕዝቡን ከኃጢአታቸው ያድናቸዋልና፡፡”

3) ኢየሱስን ስንቀበል ከእግዚአብሔር ጋር የምንገናኝበት መንገድ ነው፡፡

● ዮሐ.1÷12

12. ነገር ግን ኢየሱስ ራሱ ለተቀበሉትና በስሙ ላመኑት ሁሉ የእግዚአብሔር ልጆች የመሆን መብት ሰጣቸው፡፡

4) ኢየሱስ ክርስቶስን ስንቀበል መንፈስ ቅዱስ ወደ እኛ ይመጣል፡፡ ይህ ማለት ድነናል ማለት ነው፡፡

● ዮሐ.14÷16, 26-27

16. እኔም አብን እለምናለሁ፣ እርሱም ከእናንተ ጋር ለዘላለም የሚኖር ሌላ አጽናኝ ይሰጣችኋል፣

26. አብ በእኔ ስም የሚልከው አጽናኙ መንፈስ ቅዱስ ግን ሁሉን ነገር ያስተምራችኋለሁ፣ እኔ የነገርኳችሁንም ሁሉ እንድታስታውሱ ያደርጋችኋል፡፡

27. “ሰላምን እተውላችኋለሁ፣ ሰላሜንም እሰጣችኋለሁ፣ እኔ የምሰጣችሁ ሰላም ዓለም እንደሚሰጠው ዐይነት አይደለም፣ ልባችሁ አይጨነቅ፣ ደግሞም አይፍራ፡፡

5) በዚህ ጊዜ የሰይጣን ሥልጣን ለዘላለም ተውን ማለት ነው፡፡

● ቆላ.1÷13

13-እርሱ ከጨለማ ኀይል አድኖ ወደ ተወደደው ልጁ መንግሥት እንድንገባ አድርጎናል፡፡

6. እግዚአብሔር ከዳነ ሰው ጋር ለዘላለም ይኖራል፡፡

1) የዳነውን ሰው መንፈስ ቅዱስ ያስተምራል።

● ዮሐ.14÷26

26. አብ በእኔ ስም የሚልከው አጽናኙ መንፈስ ቅዱስ ግን ሁሉን ነገር ያስተምራችኋለሁ፣ እኔ የነገርኳችሁንም ሁሉ እንድታስታውሱ ያደርጋችኋል፡፡

2) ሁል ጊዜ ሳይተው እስከ ዓለም መጨረሻ ድረስ ከእነርሱ ጋር ይኖራል፡፡

● ማቴ.28÷20

20-እኔ ለእናንተ ያዘዝኋችሁን ሁሉ እንዲጠብቁ አስተምሯቸው፣ እነሆ፣ እኔም እስከ ዓለም መጨረሻ ድረስ ሁልጊዜ ከእናንተ ጋር ነኝ፡፡”

3) ሕይወቱን በሙሉ መንፈስ ቅዱስ ስለሚመራ፡፡

በሥጋ ፈቃድ ሳንከተል በመንፈስ ቅዱስ ፈቃድ ስንከተልና የእግዚአብሔር ቃልን ስንታዘዝ መንፈስ ቅዱስ ይመራናል፡፡

● ሮሜ.8÷14

14. በእግዚአብሔር መንፈስ የሚመሩ ሁሉ የእግዚአብሔር ልጆች ናቸው፡፡

4) የፀሎታችንን መልስ መንፈስ ቅዱስ ተቀብሎ በሥልጣን ስለሚመጣ፡፡

በፀሎት ጊዜ መልስ አለ። ከመንፈስ ቅዱስ ሥልጣን ይመጣል::

● ዮሐ.16÷24

24. እስከ አሁን እናንተ በስሜ ምንም ነገር አለመናችሁም፣ ለምኑ ይሰጣችኋል፣ ደስታችሁም ፍጹም ይሆናል፡፡

ለምሳሌ፡- የአሸናፊ ስብሰባ

ሰይጣን ውሸታምና አታላይ ነው፡፡ ሰይጣን በእኛ አዕምሮ ውስጥ የውሸትን ነገር ያስቀምጣል፡፡እኛ ደህንነት እንዳንቀበል ያታልላል፡፡ ደግሞም ሰይጣን፤ እኛ በኢየሱስ

ከመጀመርያው ኃጢአት ይቅርታ የተቀበልነውን የአሸናፊነትን ህይወት ያታልላል፡፡ ከእግዚአብሔር ጋር ሁልጊዜ እንዳይኖር ያታልላል፡፡

በክፍት ስብሰባ የሚሰጠው ቃል ቀላል ነው፡፡ በተከታታይ ለወንጌል እስከ መኖር ድረስ የሚያደርግ ስብከት ነው፤ ወንጌል በህይወት ዘመናችን ሙሉ እንድንሰብክ የተሰጠ ነው፡፡ይህን ማወቅ አስፈላጊ ብቻ ሳይሆን አሁን በህይወት እየኖርን ነን ወይ? እያልን ራሳችንን በመጠየቅ የምንተገብርበት ዋና ምክንያት ነው፡፡ በእኛ ምትክ ኢየሱስ ሞቶ ከኃጢአታችን አነፃ፤ ኃጢአት ስናደርግ የኢየሱስ ደም ከኃጢያት ሁሉ ያነፃል፡፡ እኛ በኢየሱስ ክርስቶስ በኩል አሸናፊዎች ነን፡፡

ከእግዚአብሔር ጋር እስከ መጨረሻ ድረስ እንድንኖርና ቃሉን እንድንሰብክ ሰጠን፡፡ ይህም የተሰጠው ቃል ውሸታሙን ሰይጣን እንድንከላከል ነው፡፡ በጦርነትም ጊዜ እኛ አሸናፊዎች እንሆናለን፡፡ ምክንያቱም ኢየሱስ አሸናፊ ስለሆነ እኛንም አሸናፊዎች ያደርገናል፤ክብርና ምስጋና ለእርሱ ይሁን፡፡

ምዕራፍ 14

14. አንተ አዳኙን ኢየሱስ ክርስቶስን አውቀሃል?

● ዮሐንስ 14÷6

ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰለት፣ “መንገድና እኑት ሕይወትም እኔ ነኝ፣ በእኔ በኩል ካልሆነ በቀር ማንም ወደ አብ የሚመጣ የለም፡፡

ብዙ ሰዎች ሃይመኖትን አንድ አይነት አድርገው ያስባሉ፤ የራሳቸውን ሃይማኖት በደንብ ቢያምኑ እንደሚያድን አድርገው ያስባሉ፡፡ ነገር ግን ሁሉ ሃይማኖት ደህንነትን አይሰጥም፤ ምክንያቱም ደህንነትን የሚሰጥ ኢየሱስ ክርስቶስ ብቻ ነው፡፡ እርሱን ማመን ለደህንነት በቂ ነው፡፡ የተለያዩ ሃይማኖቶች የሰው ሥራ መሠረት ነው፡፡ ነገር ግን በኢየሱስ ክርስቶስ ስም የሚያምን ሃይማኖት (ክርስትና) ከእግዚአብሔር ጋር ለዘላለም እንዲኖር የሚያደርግ ፀጋን ይሰጣል፡፡ ይህ እምነት የእግዚአብሔር ስጦታ ነው፡፡

1. ሰዎች ደህንነት ለመቀበል የሚያደርጉት ስህተት ምንድን ነው?

1) መልካም ሥራ እየሠሩ መኖር የሃይማኖት ግብ ነው ብለው ማሰብ

ብዙ ሰዎች ወደ ሃይማኖታቸው በመሄድ መልካም ሥራ ያደርጋሉ፤ ነገር ግን ደህንነትን አያገኙም፡፡

● ሮሜ.3÷20

20. ስለዚህ ሕግን በመጠበቅ ማንም በእርሱ ፊት ጻድቅ ነው ሊባል አይችልም፤ ይልቁንም በሕግ አማካይነት ኀጢአትን እንገነዘባለን፡፡

2) ብዙ ጊዜ ለደሃዎች ገንዘብ በመስጠት መርዳት የደህንነት መንገድ ነው ብለው ማሰብ፤

ነገር ግን በልብ ለተከታታይ ኃጢአት ይጨምራል:: ልቡ የሚመስል

● ኢሳ.64÷6

6-ሁላችን እንደ ርኩስ ሰው ሆነናል፥ ጽድቃችንም ሁሉ እንደ መርገም ጨርቅ ነው ሁላችንም እንደ ቅጠል ረግፈናል፥ በደላችንም እንደ ነፋስ ወስዶናል።

3) ሰዎች ኢየሱስን ማመን (ክርስቲያን መሆን) ከብዙ ሐይማኖቶች እንደ አንዱ ነው ብሎ ማሰብ

ነገር ግን ኢየሱስ ክርስቶስን ማመን (ክርስቲያን መሆን) ሃይማኖት ብቻ ሳይሆን ሕይወትን የሚሰጥ ነው፡፡

● 1ጴጥ.3÷18

18-ክርስቶስም ራሱ ወደ እግዚአብሔር ያቀርበን ዘንድ እርሱ ጻድቅ ሆኖ ሳለ ጽድቅ ለሌለን ለእኛ በኃጢአታችን ምክንያት በማያዳግም ሁኔታ አንድ ጊዜ መከራን በመቀበል ሞቶአል፤ እርሱ በሥጋ ሞተ፤ በመንፈስ ግን ሕያው ሆነ፡፡

4) ሰዎች ሰው በሚወልድበት ጊዜ ጥሩ ልብ እንዲኖር ይፈልጋሉ።

● ዘፍ.8÷21

21-የመሥዋዕቱም መዓዛ እግዚአብሔርን ደስ አሰኘው፤ በሐሳቡም እንዲህ አለ፣ ገና ከሕፃንነቱ ጊዜ ጀምሮ የሰው ሐሳብ ክፉ መሆኑን ስለማውቅ፤ "ሰው በሚፈጽመው በደል ሁሉ ከእንግዲህ ወዲህ ምድርን አልረግምም፤ በአሁኑ ጊዜ እንዳደረግሁት ሕይወት ያለውን ፍጥረት ሁሉ ከእንግዲህ ወዲህ ከቶ አላጠፋም፡፡

● ሮሜ.3÷10

10. እንዲህ ተብሎ እንደ ተጻፈ፤ "ጻድቅ ማንም የለም፤ አንድም እንኳ፤

5) ከሞት በኋላ መንግስተ ሰማይና ሲኦል የለም ብለው መሰብ

● ሉቃ. 16÷19-31

19. ደግሞ ኢየሱስ እንዲህ አለ፣ "ሐምራዊና ቀጭን ልብስ የሚለብስ አንድ ሀብታም ሰው ነበር፣ እርሱም በየቀኑ በቅንጦት ይኖር ነበር፡፡

20. በአንጻሩም መላ ሰውነቱ በቍስል የተወረረ አንድ አልዓዛር የሚባል ድኻ በዚህ በሀብታም ሰው ቤት ደጃፍ ተኝቶ ነበር፣

21. አልዓዛር ከሀብታሙ ሰው ማእድ የወደቀውን ፍርፋሪ እየለቀመ ሊመገብ ይመኝ ነበር፣ ውሾችም እየመጡ ቍስሉን ይልሱ ነበር፡፡

22. ከዚህም በኋላ ድኻው ሰው ሞተ፣ መላእክትም ወደ አብርሃም ዕቅፍ ወሰዱት፣ ሀብታሙም ሰው ደግሞ ሞቶ ተቀበረ፡፡

23. ሀብታሙ ሰው በሲኦል እየተሠቃየ ሳለ፣ ቀና ብሎ ከሩቅ አብርሃምንና በዕቅፉ የነበረውን አልዓዛርን አየ፡፡

24. ሀብታሙ ሰው አብርሃምን፣ 'አብርሃም አባት ሆይ፣ ራራልኝ፣ በዚህ በእሳት ነበልባል ውስጥ በብርቱ እሠቃያለሁና አልዓዛር የጣቱን ጫፍ ውሃ ነክሮ ምላሴን እንዲያቀዘቅዝልኝ እባክህ ላክልኝ' እያለ ጮኸ፡፡

25. አብርሃም ግን እንዲህ አለው፣ 'ልጄ ሆይ፣ አንተ በምድራዊ ሕይወትህ ዘመን መልካም ነገሮችን እንደ ተቀበልህ፣ አልዓዛርም ክፉ ነገሮችን እንደ ተቀበለ አስታውስ፣ አሁን ግን አልዓዛርም እዚህ ሲጽናና፣ አንተ በሥቃይ ላይ ትገኛለህ፡፡

26.ከሁሉም በላይ ከዚህ ወደ እናንተ ለማለፍ የሚፈልጉ እንደማይችሉ፣ እዚያ ያሉትም ደግሞ ወደ እኛ እንዳይሻገሩ፣ በእኛ እናንተም መካከል ትልቅ ገደል ተደርጎአል፡፡

27. ሀበታሙም እንዲህ አለ፣ 'አባት ሆይ፣ እንግዲያውስ እባክህ አልዓዛርን ወደ አባቴ ቤት እንድትልከው እለምንሃለሁ፣

28. ለእኔ አምስት ወንድሞች ስላሉኝ፣ አልዓዛር ሄዶ እነርሱ ወደዚህ የሥቃይ ስፍራ እንዳይመጡ ያስጠንቅቃቸው፡፡

29. አብርሃም ግን እንዲህ አለው፣ 'ለእነርሱ ሙሴና ነቢያት አሏቸው፣ እነርሱን ይስሙ'

30. ሀብታሙም ሰው፣ 'አባት አብርሃም ሆይ፣እንደዚህ አይደለም፤ አንድ ሰው ከሙታን ተነሥቶ ቢሄድላቸው ንስሓ ይገባሉ' አለ፡፡

31. አብርሃምም፣ 'እነርሱ ሙሴንና ነቢያትን የማይሰሙ ከሆነ፣ አንድ ሰው ከሙታን ቢነሣ እንኳ እነርሱ አያምኑም' አለው፡፡

2. እነዚህ ሰዎች ኃጢአት ምን እንደሚያደርግ አያውቁም፡፡

1) የኃጢአት ውጤት የሰውን ልብ ማበላሸት ነው፡፡

● ኤር.17÷9

የሰው ልብ ከሁሉ ይልቅ ተንኰለኛ እጅግም ክፉ ነው ማንስ ያውቀዋል?

2) ሰው በመንፈስ ሙት ሆነ፡፡

● ኤፌ.2÷1

1-እናንተ በበደላችሁና በኃጢአታችሁ ምክንያት በመንፈሳዊ ኑሮአችሁ የሞታችሁ ነበራችሁ፤

3) ሰዎች በክፉ መናፍስት ተይዘው ባርያ ሆኑ፡፡ ኃጢአት ሰዎች ለጠንቋይና ለጣኦት ባሪያ እንዲሆኑ ያደርጋል፡፡

● ኤፌ.2÷2

2-በዚያን ጊዜ የዚህን ዓለም ክፉ አካሄድ ትከተሉ ነበር፤ እንዲሁም በአየር ላይ ያሉትን የመናፍስት ኀይሎች ለሚገዛው ትታዘዙ ነበር፤ እርሱ በማይታዘዙት ሰዎች ላይ የሚሠራ ርኩሱ መንፈስ ነው፡፡

4) በውድቀት (በጥፋት) ውስጥ እንዲገቡ ያደርጋል፡፡ (እንደ ሌሎች የቁጣ ልጆች ነበርን፡፡)

● ኤፌ.2÷3

3-እኛም ሁላችን ከዚህ በፊት በእነርሱ መካከል የሥጋችንን ፈቃድና የአእምሮአችንን ሐሳብ እየተከተልን በሥጋችን ምኞት እንኖር ነበር፤ እንደ ሌሎቹም በተፈጥሮአችን በእግዚአብሔር ቊጣ ሥር ነበርን፡፡

5) በሰይጣን መንፈስ ቁጥጥር ስርና በርግማን ውስጥ እንድኖሩ ያደርጋል፡፡ ጣኦትንና ጠንቋይን ማገልገል በሰይጣን ምሪት ውስጥ መሆን ማለት ነው፡፡

● ዮሐ.8÷44

44. እናንተ የአባታችሁ የዲያብሎስ ልጆች ናችሁ፣ የአባታችሁንም ፍላጎት ለመፈጸም ትሻላችሁ፡፡ እርሱ ከመጀመሪያ ነፍሰ ገዳይ ነበር፣ በዲያብሎስ እውነት ስለሌለ በእውነት አልቆመም፣ ዲያብሎስ ሐሰተኛና የሐሰት አባት ስለ ሆነ ሐሰት በሚናገርበት ጊዜ ከገዛ ራሱ አውጥቶ ይናገራል፡፡

6) ይህን ሳያውቁ በተከታታይ ለጣኦትንና ለጠንቋይ በማገልገል ህመምን ይቀበላሉ እንጂ ደህንነትን ሳያገኙ በመጨረሻ ወደ ጥፋት ይሄዳሉ፡፡

● ሮሜ.1÷21-23

21. እንግዲህ አንተ ሌሎችን የምታስተምር፣ ራስህን አታስተምርምን? አትስረቅ ብለህ የምትሰብክ፣ ትሰርቃለህን?

22. አንተ ሰዎች ማመንዘር የለባቸውም የምትል፣ ታመነዝራለህን? አንተ ጣዖትን የምትጸየፍ፣ ቤተ መቅደስን ትመዘብራለህን?

23. አንተ በሕግ የምትመካ፣ ሕግን በመተላለፍ እግዚአብሔርን ታዋርዳለህን?

7) እርግማን ከ3ኛ-4ኛ ትውልድ ይደርሳል፡፡

● ዘፀ.20÷4-5

4-በ"ሰማይም ሆነ በምድር ወይም ከምድር በታች ባለው ውሃ ውስጥ ከሚኖሩት ነገሮች የማንኛውንም ዐይነት ምስል ጣዖት አድርገህ አትሥራ፤

5-እኔ እግዚአብሔር አምላክህ እጅግ ቀናተኛ ስለ ሆንኩ ተቀርጾ የተሠራውን ማንኛውም ጣዖት አታምለክ፤ አትስገድለትም፤ እኔ የሚጠሉኝን ሁሉ እቀጣለሁ፤ ዘራቸውንም ሁሉ እስከ ሦስትና አራት ትውልድ ድረስ እበቀላለሁ፡፡

8) በመጨረሻ ጊዜ ወደ ሲኦል ያስወስዳል፡፡

● ራዕ.21÷8

8-ነገር ግን ፈሪዎች፣ እመነት ቢሶች፣ ርኩሶች፣ ነፍሰ ገዳዮች፣ አመንዝሮች፣ አስማተኞች፣ ጣዖት አምላኪዎች ውሸታሞች ሁሉ ዕጣ ክፍላቸው በዲን በሚቃጠለው በእሳት ባሕር ውስጥ ይሆናል፤ ይህ ሁለተኛው ሞት ነው፡፡"

3. መንፈሳዊ ሰው በመጀመሪያ ለመንፈሳዊ ነገር መኖር ያስፈልጋል፡፡

1) በመንፈሳዊ ነገር ሙት መሆን በሰይጣን ቁጥጥር ስር ሆነ ማለት ነው፡፡

● ዮሐ.8÷44

44. እናንተ የአባታችሁ የዲያብሎስ ልጆች ናችሁ፤ የአባታችሁንም ፍላጎት ለመፈጸም ትሻላችሁ፡፡ እርሱ ከመጀመሪያ ነፍሰ ገዳይ ነበር፤ በዲያብሎስ እውነት ስለሌለ በእውነት አልቆመም፤ ዲያብሎስ ሐሰተኛና የሐሰት አባት ስለ ሆነ ሐሰት በሚናገርበት ጊዜ ከገዛ ራሱ አውጥቶ ይናገራል፡፡

2) ስለዚህ ሳያወቀው በሰይጣን እጅ ተይዞ ባሪያ ይሆናል፡፡

● ኤፌ.2÷3

3-እኛም ሁላችን ከዚህ በፊት በእነርሱ መካከል የሥጋችንን ፈቃድና የአእምሮአችንን ሐሳብ እየተከተልን በሥጋችን ምኞት እንኖር ነበር፤ እንደ ሌሎቹም በተፈጥሮአችን በእግዚአብሔር ቍጣ ሥር ነበርን፡፡

3) ባሪያ ማለት በጠንቋይና በጣኦት እጅ ገብቶ መኖር ማለት ነው፡፡

● ኤፌ.2÷2

2-በዚያን ጊዜ የዚህን ዓለም ክፉ አካሄድ ትከተሉ ነበር፤ እንዲሁም በአየር ላይ ያሉትን የመናፍስት ኀይሎች ለሚገዛው ትታዘዙ ነበር፤ እርሱ በማይታዘዙት ሰዎች ላይ የሚሠራ ርኩሱ መንፈስ ነው፡፡

4) መንፈሳዊ ዕውቀት ስላላወቁ ሰይጣንን ያገለግላሉ፡፡ በመሥዋዕት አያቶችህ እንዳገለገሉ ሳይሆን ሰይጣን አንተን በቀጥታ አግኝቶ እርሱን እንዲያገለግል ያደርጋል፡፡

● 1ቆሮ.10÷20

20- አሕዛብ መሥዋዕት የሚያቀርቡት ለእግዚአብሔር ሳይሆን ለአጋንንት ነው፤ ስለዚህ እናንተ ከአጋንንት ጋር ኅብረት እንዲኖራችሁ አልፈልግም፤

● ሮሜ.8÷2

2. በክርስቶስ ኢየሱስ የሚገኘውን ሕይወት የሚሰጥ የመንፈስ ቅዱስ ሕግ ከኃጢአትና ከሞት ሕግ ነጻ አውጥቶኛል፡፡

1ቆሮ.10÷20 “አህዛብ የሚሰውት ለእግዚአብሔር ሳይሆን ለአጋንንት (ሰይጣን)ነው፡፡” ሮሜ.8÷2 ምክንያቱም የህይወት መንፈስ ህግ በክርስቶስ ኢየሱስ

ከኃጢአትና ከሞት ህግ ነፃ አውጥቶአቸዋል፡፡ ኢየሱስን ቢያምኑ ከጠንቋይ ከጣኦት ከኃጢያት ከሞትና ከሰይጣን ነፃ ይወጣሉ፡፡

5) ከእግዚአብሔር ጋር ለመገናኘት አስቀድሞ በመንፈሳዊ ህይወት መኖር ያስፈልጋል፡፡

- ሮሜ.8÷1-2

1. ስለዚህ በክርስቶስ ኢየሱስ የሚኖሩ አሁን ኵነኔ የለባቸውም፡፡

2. በክርስቶስ ኢየሱስ የሚገኘውን ሕይወት የሚሰጥ የመንፈስ ቅዱስ ሕግ ከኃጢአትና ከሞት ሕግ ነጻ አውጥቶኛል፡፡

4. በኢየሱስ በኩል እኛ ከእግዚአብሔር ጋር መገናኘት እንችላለን፡፡

1) ኢየሱስ ለሰው ሀዘን መፍትሄ የሚሰጥ ነው፡፡

ኢየሱስ ወደ ምድር የመጣበት ምክንያት የሰይጣንን ሥራ ለማፍረስ ነው፡፡

- 1 ዮሐ.3÷8

8. ዲያብሎስ ከመጀመሪያው አንሥቶ ኃጢአት ስለሚሠራ ኃጢአትን የሚሠራ ሁሉ የዲያብሎስ ወገን ነው፡፡ የእግዚአብሔር ልጅ የተገለጠውም የዲያብሎስን ሥራ ለማፍረስ ነው፡፡

2) ኢየሱስ የሰውን ሥጋ ሰብሶ የመጣ እግዚአብሔር ነው፡፡

(ፊልጵ.2÷6-8) “ደም ሳይፈስስ ስርየት የለም” ይህ ማለት ኢየሱስ ስለኃጢአተኞች የራሱን ደም ለማፍሰስ መጣ ማለት ነው፡፡

- ፊልጵ.2÷6-8

6-እርሱ ሁልጊዜ የመለኮት ባሕርይ አለው፡፡ ይሁን እንጂ ከእግዚአብሔር ጋር እኩል የሚያደርገውን የመለኮት ባሕርይ በኃይል እንደ ያዘ አልቈጠረውም፡፡

7-ይልቁንም ያለውን ክብር ሁሉ ትቶ እንደ ባሪያ ሆኖ ታየ እንደ ሰውም ተወለደ፤ በሰው አምሳልም ተገለጠ፤

8-በትሕትና ራሱን ዝቅ አደረገ፤ እስከ ሞት ድረስ፣ ያውም በመስቀል ላይ ተሰቅሎ እስከ መሞት ድረስ ታዛዥ ሆነ፡፡

3) ኢየሱስ በኃጢአታችን ፋንታ ሞቶ ይቅርታን ሰጠ፡፡

● ዮሐ.1÷29

29. በማግስቱ ዮሐንስ ኢየሱስን ወደ እርሱ ሲመጣ አይቶ እንዲህ አለ፤ “እነሆ፣ የዓለምን ኃጢአት የሚያስወግድ የእግዚአብሔር በግ ይህ ነው!

4) ይህ ለኃጢአት ሁሉና ለርግማኔ መፍትሄ የሚሆን ነው፡፡ ኢየሱስ ኃጢአታችንና እርግማኔአችንን ተቀብሎ ለእኛ የአብርሃም በረከቶችን ሰጠ፡፡

● ገላ.3÷13-14

13-“በእንጨት ላይ ተሰቅሎ የሚሞት ሁሉ የተረገመ ነው” ተብሎ ስለ ተጻፈ ክርስቶስ ስለ እኛ እንደ ተረገመ ሰው ሆኖ ሕግ ከሚያስከትለው ርግማን ዋጀን፡፡

14-ይህም የሆነው እግዚአብሔር ለአብርሃም የሰጠው በረከት በኢየሱስ ክርስቶስ አማካይነት ለአሕዛብ እንዲደርስና እኛም እግዚአብሔር እሰጣችኋለሁ ያለውን መንፈስ ቅዱስን በእምነት እንድንቀበል ነው፡፡

★ የአብርሃም ረከቶች

① የእያንዳንዱ ሰው መባረክ

② በቤተሰብ (አባት እናት ልጆች) ወዘተ . . . መባረክ

③ በዘመዶች መባረክ

④ በአገር (በሚኖርበት አካባቢ መባረክ)

⑤ በሁሉ ቦታ (በአለም በሁሉመባረክ )

ኢየሱስ የመንፈስ ቅዱስ ስጦታ ሰጥተአል፡፡

★ ኢየሱስ

① የእኛን ኃጢአት በሁሉ በመሸከም መፍትሔ ሰጠ::

② የአብርሃምን ረከቶች ሰጠ::

③ መንፈስ ቅዱስን ሰጠ::

5) ይህ ለእኛ የሚገልፀው የእግዚአብሔርን ፍቅር ነው፡፡

● ሮሜ. 5÷8

8. ነገር ግን እኛ ኃጢአተኞች ሆነን ሳለ ክርስቶስ በእኛ ምትክ ሞቶአል፤ ይህም እግዚአብሔር ለእኛ ያለው ፍቅር ምን ያህል ታላቅ መሆኑን ያስረዳል፡፡

● ዮሐ. 3÷16

16-"በእርሱ የሚያምን ሁሉ የዘለዓለም ሕይወት እንዲኖረው እንጂ እንዳይጠፋ እግዚአብሔር ዓለምን እጅግ ስለ ወደደው አንድያ ልጁን ሰጠ፡፡

5. ኢየሱስ ብቻ ከእግዚአብሔር ጋር የምንገናኝበት መንገድ፣ እውነትና ሕይወት ነው፡፡

1) ኢየሱስ ክርስቶስን አዳኝና ጌታ አድርገህ ተቀበል፡፡

● ዮሐ.1÷12

12. ነገር ግን ኢየሱስ ራሱ ለተቀበሉትና በስሙ ላመኑት ሁሉ የእግዚአብሔር ልጆች የመሆን መብት ሰጣቸው፡፡

2) ኢየሱስ የሚያምኑትን ከጥፋትና ከርግማን ነፃ ያወጣል፡፡

ኢየሱስ ለሚያምኑ ሰዎች ሁሉ ኃጢአታቸውን ደምስሶ መፍትሄ የሚሰጥ ነው፡፡

● ኤፌ.2÷1-3

1-እናንተ በበደላችሁና በኃጢአታችሁ ምክንያት በመንፈሳዊ ኑሮአችሁ የሞታችሁ ነበራችሁ፤

2-በዚያን ጊዜ የዚህን ዓለም ክፉ አካሄድ ትከተሉ ነበር፤ እንዲሁም በአየር ላይ ያሉትን የመናፍስት ኀይሎች ለሚገዛው ትታዘዙ ነበር፤ እርሱ በማይታዘዙት ሰዎች ላይ የሚሠራ ርኩስ መንፈስ ነው፡፡

3-እኛም ሁላችን ከዚህ በፊት በእነርሱ መካከል የሥጋችንን ፈቃድና የአእምሮአችንን ሐሳብ እየተከተልን በሥጋችን ምኞት እንኖር ነበር፤ እንደ ሌሎቹም በተፈጥሮአችን በእግዚአብሔር ቍጣ ሥር ነበርን፡፡

3) ኢየሱስ ለሚያምኑት ሁሉ ከሰይጣን ስልጣን፣ ከጣኦት፣ ከጠንቋይና ከመጥፎ እድል ሁሉ ወዲያውኑ ነፃ ያወጣል፡፡

● ሐዋ.10÷38

38-እግዚአብሔር የናዝሬቱን ኢየሱስ በመንፈስ ቅዱስና በኀይል ቀባው፤ ኢየሱስ መልካም ነገርን እያደረገ በዲያብሎስ የተያዙትን ሁሉ ፈወሰ፤ እግዚአብሔርም ከኢየሱስ ጋር ነበር፡፡

4) ኢየሱስን የሚያምኑ ቢሞቱም እንኳን ከፍርድ ነፃ ያወጣል፡፡

● ዕብ.9÷27

27-ለሰው አንድ ጊዜ መሞት ተመድቦለታል፤ ከሞት በኋላም ፍርድ አለበት፡፡

5) ኢየሱስ ክርስቶስን ያመኑ አሁን በምኖሩበት ጊዜ በረከት ወደ ፊት ደግሞ የዘላለም ሕይወትን ይቀበላሉ፡፡

● ገላ.3÷13-14

13-“በእንጨት ላይ ተሰቅሎ የሚሞት ሁሉ የተረገመ ነው” ተብሎ ስለ ተጻፈ ክርስቶስ ስለ እኛ እንደ ተረገመ ሰው ሆኖ ሕግ ከሚያስከትለው ርግማን ዋጀን፡፡

14-ይህም የሆነው እግዚአብሔር ለአብርሃም የሰጠው በረከት በኢየሱስ ክርስቶስ አማካይነት ለአሕዛብ እንዲደርስና እኛም እግዚአብሔር እሰጣችኋለሁ ያለውን መንፈስ ቅዱስን በእምነት እንድንቀበል ነው፡፡

● ቆላ.1÷13

13-እርሱ ከጨለማ ኀይል አድኖ ወደ ተወደደው ልጁ መንግሥት እንድንገባ አድርጎናል፡፡

አዲስ ሰው ወደ ክፍት ስብሰባ ሲመጣ ኢየሱስን እንዲቀበል አድርግ፡፡

6. ኢየሱስ ክርስቶስን ያመኑ ሰዎች ልዩ ሥልጣንን ይቀበላሉ፡፡

1) የእግዚአብሔር ልጅ መሆን ልዩ ሥልጣን ነው፡፡

- ዮሐ.1÷12

12. ነገር ግን ኢየሱስ ራሱ ለተቀበሉትና በስሙ ላመኑት ሁሉ ሰዎች የእግዚአብሔር ልጆች የመሆን መብት ሰጣቸው፡፡

- ሮሜ.8÷14-15

14. በእግዚአብሔር መንፈስ የሚመሩ ሁሉ የእግዚአብሔር ልጆች ናቸው፡፡

15. ስለዚህ፣ "አባ! አባታችን ሆይ!" ብላችሁ የምትጠሩበትን የልጅነት መንፈስ ተቀበላችሁ እንጂ በፍርሃት ለመኖር እንደገና የባርነትን መንፈስ አልተቀበላችሁም፡፡

2) የፀሎት መልስ መቀበል ልዩ ሥልጣን ነው፡፡

በእግዚአብሔር ልጅ በኢየሱስ ስም ብቻ የምንፀልየውን ፀሎት ልዩ ሥልጣን ነው እኛ ከእግዚአብሔር ጋር የመኖራችን ምስክር የፀሎት መልስ መቀበል ነው፡፡

- ዮሐ.16÷24

24. እስከ አሁን እናንተ በስሜ ምንም ነገር አለመናችሁም፣ ለምኑ ይሰጣችኋል፣ ደስታችሁም ፍጹም ይሆናል፡፡

3) የሰይጣንን ሥልጣን ማሸነፍ ልዩ ሥልጣን ነው፡፡

- ማር.16÷17

17. የሚያምኑትም እነዚህን ምልክቶች ያደርጋሉ፣ በስሜ አጋንንትን ያወጣሉ፣ በአዲስ ልሳንም ይናገራሉ፣

4) የመላዕክት ዕርዳታ መቀበል ልዩ ሥልጣን ነው፡፡

● ዕብ.1÷14

14-ታዲያ፣ መላእክት ሁሉ የሚድኑትን ሰዎች ለማገልገል የሚላኩ የእግዚአብሔር አገልጋዮች የሆኑ መናፍስት አይደሉምን?

5) አጽናኙ መንፈስ ቅዱስ ከእኛ ጋር መኖር ልዩ ሥልጣን ነው፡፡

● ዮሐ.14÷16-17

16. እኔ አብን እለምናለሁ፣ እርሱም ከእናንተ ጋር ለዘላለም የሚኖር ሌላ አጽናኝ ይሰጣችኋል፣

17. እርሱም የእውነት መንፈስ ነው፣ ዓለም እርሱን ስለማያየውና ስለማያውቀው ሊቀበለው አይችልም፡፡ እናንተ ግን፣ እርሱ ከእናንተ ጋር ስለሚኖርና በውስጣችሁ ስላለ ታውቁታላችሁ፡፡

6) ዓለምን የሚያሸነፍ ሥልጣን መቀበል ልዩ ሥልጣን ነው፡፡

● ማቴ.28÷18-20

18-ኢየሱስ ወደ ደቀ መዛሙርቱ ቀረበና እንዲህ አላቸው፣ “ሥልጣን ሁሉ በሰማይና በምድር ተሰጥቶኛል፣

19-ስለዚህ እናንተ ወደ ዓለም ሕዝብ ሁሉ ሂዱ፣ በአብ፣ በወልድና በመንፈስ ቅዱስ ስም እያጠመቃችኋቸው የእኔ ደቀ መዛሙርት አድርጉአቸው፡፡

20-እኔ ለእናንተ ያዘዝኋችሁን ሁሉ እንዲጠብቁ አስተምሯቸው፣ እነሆ፣ እኔም እስከ ዓለም መጨረሻ ድረስ ሁልጊዜ ከእናንተ ጋር ነኝ፡፡”

7) ራዕያችንን ለዓለም ስናደርግ

① ኢየሱስ በመስቀል ላይ ያሸነፈውን ይዘን ወንጌልን ልንሰብክ ያስፈልጋል፡፡

② የመንፈስ ቅዱስ ሥራ ልንለማመድ ያስፈልጋል፡፡ (ሐዋ.ምዕ 1 - ምዕ 2)

③ በክፍት ስብሰባ በኩል ራዕያችንን ለዓለም ማድረስ ይቻላል፡፡

ፀሎት፡- እኛ የወንጌልን ሥራ ልንለማመድና በዚህ አካባቢ የክፍት ስብሰባ እንድበዛ ልንፀልይ ያስፈልጋል፡፡ በፀሎት ሁሉ ይቻላል፡፡

ምዕራፍ 15

15. በፀሎት ሁሉም ነገር ይቻላል፡፡ (ፊልጵ.4÷6-7)

● ፊልጵ.4÷6-7

6-ጌታ ቅርብ ነው። በነገር ሁሉ በጸሎትና በምልጃ ከምስጋና ጋር በእግዚአብሔር ዘንድ ልመናችሁን አስታውቁ እንጂ በአንዳች አትጨነቁ።

7-አእምሮንም ሁሉ የሚያልፍ የእግዚአብሔር ሰላም ልባችሁንና አሳባችሁን በክርስቶስ ኢየሱስ ይጠብቃል።

በእግዚአብሔር ልጅ በኢየሱስ ስም ብንፀልይ ሁሉንም ነገር መቀበል እንችላለን፡፡ በእግዚአብሔር ልጅ በኢየሱስ ስም ብንፀልይ እግዚአብሔር ለእኛ መልስ ይሰጣል፡፡ ፀሎት ለሁሉም ችግሮች መፍትሄ የሚሰጥ ነው፡፡ በምንኖርበት አካባቢ በየቀኑ የፀለይነውን የፀሎት መልስ የሚንቀበል ሰዎች ልንሆን ይገባል፡፡

እንዴት ብንፀልይ ምላሽ ይመጣል?

1) የእግዚአብሔር ልጆች ሆነን ብንፀልይ መልስ ይመጣል፡፡

● ዮሐ.1÷12

12. ነገር ግን ኢየሱስ ራሱ ለተቀበሉትና በስሙ ላመኑት ሁሉ ሰዎች የእግዚአብሔር ልጆች የመሆን መብት ሰጣቸው፡፡

2) በኢየሱስ ክርስቶስ ሽም ብንፀልይ መልስ ይመጣል፡፡

● ዮሐ.16÷24

24. እስከ አሁን እናንተ በስሜ ምንም ነገር አለመናችሁም፣ ለምኑ ይሰጣችኋል፣ ደስታችሁም ፍጹም ይሆናል፡፡

3) ኃጢአታችንን ተናዝዘን ብንፀልይ መልስ ይመጣል፡፡

● መዝ.66÷18

18-በልቤስ በደልን አይቼ ብሆን ጌታ አይሰማኝም ነበር።

4) መልስ እስኪመጣ ድረስ በእምነትና በትዕግስት ብንጠብቅ መልስ ይመጣል፡፡

● ሉቃ.18÷1-8

1. ኢየሱስ ለደቀ መዛሙርቱ ሳይታክቱ ሁል ጊዜ መጸለይ እንደሚገባቸው ለማስተማር ይህን ምሳሌ ነገራቸው፤

2. “በአንዲት ከተማ የሚኖር እግዚአብሔርን የማይፈራና ሰውን የማያከብር አንድ ዳኛ ነበረ፡፡

3. በዚያችው ከተማ የምትኖር አንዲት መበለት ነበረች፤ እርሷ ወደ ዳኛው እየመጣች፤ ‘ከባላጋራዬ ጋር ስላለኝ ክርክር ፍርድ ስጠኝ!’ ትለው ነበር፡፡

4. ዳኛውም ፍርድ ለመስጠት ብዙ ጊዜ አልተቀበላትም ነበር፤ በኋላ ግን እንዲህ ሲል አሰበ፤ ‘ምንም እግዚአብሔርን ባልፈራ፤ ሰውንም ባላከብር፤

5. ይህች መበለት ስለ ነዘነዘችኝ እፈርድላታለሁ፤ አለበለዚያ ግን ዘወትር እየተመላለሰች ታሰለቸኛለች፡፡’ ”

6. ጌታ ኢየሱስ እንዲህ አለ፤ “ዐመፀኛው ዳኛ የተናገረውን ስሙ፡፡

7. እግዚአብሔርስ ቀንና ሌሊት ወደ እርሱ ለሚጮኹ ምርጦቹ አይፈርድላቸውምን? ከመጠን በላይስ ችላ ይላቸዋልን?

8. እኔ እላችኋለሁ፤ እግዚአብሔር ፈጥኖ ለሰዎቹ ይፈርድላቸዋል፤ ነገር ግን የሰው ልጅ በሚመጣበት ጊዜ በምድር ላይ እምነትን ያገኝ ይሆንን?”

5) ለሀሳባችንና ለአዕምሮአችን ጥበብ በመስጠት መልስ ይጀምራል፡፡

● ፊልጵ.4÷6-7

6-ጌታ ቅርብ ነው። በነገር ሁሉ በጸሎትና በምልጃ ከምስጋና ጋር በእግዚአብሔር ዘንድ ልመናችሁን አስታውቁ እንጂ በአንዳች አትጨነቁ።

7-አእምሮንም ሁሉ የሚያልፍ የእግዚአብሔር ሰላም ልባችሁንና አሳባችሁን በክርስቶስ ኢየሱስ ይጠብቃል።

★ የፀሎት መልስ ቅደም ተከተል

① መንፈስ ቅዱስ በሚያስደንቅ ሁኔታ እምነትንና ስልጣንን በመስጠት ይገልፃል፡፡

● ሐዋ.1÷8

8-ነገር ግን መንፈስ ቅዱስ በእናንተ ላይ በወረደ ጊዜ ኀይልን ትቀበላላችሁ፤ በኢየሩሳሌም፣ በይሁዳ ምድር ሁሉ፣ በሰማርያ፣ እስከ ምድርም ዳርቻ ድረስ ምስክሮቼ ትሆናላችሁ፡፡”

② የሚረዳ ሰውን በመግለጥ፡፡ ጥበብን በመግለፅ ለችግሮቻችን መፍትሄ ይሰጣል፡፡

● ሐዋ.2÷19

19-እኔ በላይ በሰማይ ድንቅ ነገሮችን፣ በታች በምድር ተአምራትን አሳያለሁ፤ ደም፣ እሳት፣ የጢስ ጭጋግም ይታያል፡፡

③ በትዕግስት እንድንጠብቅ እምነትን ይሰጣል፡፡

● ዮሐ.1÷6

6. ከእግዚአብሔር የተላከ ስሙ ዮሐንስ የሚባል አንድ ሰው ነበረ፤

④ የመላዕክት እርዳታ ይበዛል፡፡

● ዕብ.11÷14

14-እንዲህ የሚናገሩ ሰዎች የራሳቸው የሚሆነውን አገር እንደሚጠባበቁ በግልጽ ያመለክታሉ፡፡

● ራዕ.8÷3-5

3-የወርቅ ጥና የያዘ ሌላ መልአክ መጣና በመሠዊያው አጠገብ ቆመ፤ በዙፋኑ ፊት ባለው የወርቅ መሠዊያ ላይ ከቅዱሳን ጸሎት ጋር የሚያቀርበው ብዙ ዕጣን ተሰጠው፡፡

4-የዕጣኑ ጢስ ከቅዱሳን ጸሎት ጋር ከመልአኩ እጅ ወደ እግዚብሔር ፊት ወጣ፡፡

5-ከዚህ በኋላ መልአኩ ጥናውን ይዞ ከመሠዊያ እሳት ሞላበትና ወደ ምድር ወረወረው፤ ነጐድጓድ፣ ድምፅ፣ መብረቅ፣ የምድር መናወጥም ሆነ፡፡

⑤ ፍላጎታችን በመውላት ያረካናል፡፡

● ያዕ.1÷5

5-ከእናንተ መካከል ጥበብ የጐደለው ሰው ቢኖር እግዚአብሔርን ይለምን፤ እግዚአብሔርም ይሰጠዋል፤ እርሱ ምንም ቅር ሳይለው ለሁሉም በልግሥና የሚሰጥ ቸር አምላክ ነው፡፡

ለፀሎታችን ታላቅ መለስ ይሰጣል፡፡

ኢየሱስ ክርስቶስን ያላመኑ ሰዎች ወደ ጣኦትና ወደ ጠንቋይ ይፀልያሉ፡፡

የእኛ ፀሎት ከእነርሱ የሚለየው በምንድን ነው?

1) ያላመኑ ሰዎች ወደ ድንጋይ፣ወደ እንጨት፣ወደ ፀሐይ፣ወደ ጨረቃ፣በወረቀት ላይ ወደ ተሳለው ስዕል፣ ወደ ተቀረፀው ምስልና ወደ እንስሳት ይፀልያሉ፡፡ እንዚህ ነገሮች ሁሉ እግዚአብሔር የፈጠራቸው ፍጡራን ናቸው፡፡ ወደ ጣኦትና ወደ ፍጡራን ቢፀልዩ ሰይጣን መጥቶ ይሰራል፡፡ ሰይጣን አታልሎ ወደ ጥፋትና ወደ ሲኦል ይወስዳል፡፡

● ሮሜ.1÷21-23

21. እነርሱ እግዚአብሔርን ዐውቀውት ሳለ ለእርሱ እንደ አምላክነቱ የሚገባውን ክብርና ምስጋና አልሰጡትም፤ በሐሳባቸውም ከንቱ ሆኑ፤ የማያስተውል ልቡናቸውም ጨለመ፤

22. “ጥበበኞች ነን” ሲሉ ሞኞች ሆኑ፡፡

23. የዘላለም አምላክን ክብር ምዉት በሆነው ሰው፣ በወፎች፣ በእንስሳትና በምድር ላይ በሚሳቡ ፍጥረት መልክ መስለው ለወጡ፡፡

2) ሰይጣን ሥልጣንን፣ ፈውስን፣ ልሳንን፣ ወዘተ. . . ይገልጣል፡፡

● ሕዝ.16÷21

21-ልጆቼን አረድሽ ለእነርሱም በእሳት በኩል አሳልፈሽ ሰጠሽ በውኑ ግልሙትናሽ ጥቂት ነውን?

3) ነገር ግን እነዚህን ማታለሎች የሰማና የሚያደርግ ሰው ወደ ሲኦል ይወርዳል፡፡

● 1ቆሮ.10÷20

20- አሕዛብ መሥዋዕት የሚያቀርቡት ለእግዚአብሔር ሳይሆን ለአጋንንት ነው፤ ስለዚህ እናንተ ከአጋንንት ጋር ኅብረት እንዲኖራችሁ አልፈልግም፤

4) የእነዚህ ውጤት እንደ ሌባ ተወስዶ ለሰይጣን ተሰጥቶ መመታትና መውደቅ ነው፡፡

● ዮሐ.10÷10

10. ሌባው ሊሰርቅ፣ ሊገድልና ሊያጠፋ ብቻ ይመጣል፣ እኔ የመጣሁት በጎቼ ሕይወት እንዲያገኙና የተትረፈረፈ ሕይወት እንዲኖራቸው ነው፡፡

ነገር ግን እግዚአብሔር በፀሎት በኩል ለእኛ ህይወትንና ብዙ በረከቶችን ለመስጠት ይፈልጋል፡፡ ከሚቀጥለው መፅሐፍ ፈልገህ አግኝ::

1) ማንኛውንም ነገር ብንለምን የመቀበል በረከት

● ዮሐ.14÷13-14

13. አብ በወልድ እንዲከብር፣ በስሜ የምትለምኑትን ሁሉ አደርገዋለሁ፣

14. ማንኛውንም ነገር በስሜ ብትለምኑ፣ እኔ አደርገዋለሁ፡፡

2) ስንለምን ስንፈልግ የማግኘትና ስናንኳኳ የመከፈት በረከቶችንና ስልጣንን መቀበል።

● ማቴ.7÷7-11

7. ለምኑ፥ ትቀበላላችሁ፤ ፈልጉ፥ ታገኛላችሁ፣ በሩን አንኳኩ፥ በሩ ለእናንተ ይከፈትላችሁማል።

8. የሚለምን ሁሉ ይቀበላል፣ የሚፈልግም ያገኛል፣ ለሚያንኳኳም በሩ ይከፈትለታል።

9. ከእናንተ መካከል ልጁ እንጀራ ቢለምነው፥ ለልጁ ድንጋይን የሚሰጠው ሰው ማን ነው?

10. ልጁ ዓሣን ቢለምነው ማን እባብን ይሰጠዋልን?

11. እንግዲህ እናንተ ክፉዎች ሳላችሁ፣ ለልጆቻችሁ መልካም ስጦታ መስጠትን ካወቃችሁ፥ ታዲያ፣ የሰማዩ አባታችሁማ ለሚለምኑት መልካም ስጦታን እንዴት አብልጦ አይሰጣቸውም?

3) ወደ ኢየሱስ ስንጮህ ታላቅና ኃይለኛ ነገር የማየት በረከት

● ኤር.33÷3

3-ወደ እኔ ጩኽ፥ እኔም እመልስልሃለሁ አንተም የማታውቀውን ታላቅና ኃይለኛ ነገርን አሳይሃለሁ።

4) አምነን የምንፈልገውን ያለ ጥርጥር የመቀበል በረከት

● ማቴ.21÷22

22-እምነት ካላችሁ በጸሎት የምትለምኑትን ሁሉ ትቀበላላችሁ፡ ፡”

5) ያለምንም ጭንቀት በፀሎትና በምስጋና ስንቀርብ የመቀበል በረከት

● ፊልጵ.4÷6-7

6-ጌታ ቅርብ ነው። በነገር ሁሉ በጸሎትና በምልጃ ከምስጋና ጋር በእግዚአብሔር ዘንድ ልመናችሁን አስታውቁ እንጂ በአንዳች አትጨነቁ።

7-አእምሮንም ሁሉ የሚያልፍ የእግዚአብሔር ሰላም ልባችሁንና አሳባችሁን በክርስቶስ ኢየሱስ ይጠብቃል።

6) በኢየሱስ ስም ስንፀልይ መልስና ደስታ የማግኘት በረከት፡ ፡

● ዮሐ.16÷24

24. እስከ አሁን እናንተ በስሜ ምንም ነገር አለመናችሁም፤ ለምኑ ይሰጣችኋል፤ ደስታችሁም ፍጹም ይሆናል፡ ፡

የጌታ ልጅ የሆነ ማንኛውም ሰው በሚፀልይበት ጊዜ ከጌታ ጋር ይነጋገርል፡ ፡

1) በኢየሱስ ስም መፀለይ በጣም አስፈላጊ ነው፡ ፡

● ዮሐ.16÷24

24. እስከ አሁን እናንተ በስሜ ምንም ነገር አለመናችሁም፤ ለምኑ ይሰጣችኋል፤ ደስታችሁም ፍጹም ይሆናል፡ ፡

2) ችግሮች ሲኖሩ ለእግዚአብሔር እንደገና መፀለይ ያስፈልጋል፡ ፡

● ዮሐ.14÷13

13. አብ በወልድ እንዲከብር፤ በስሜ የምትለምኑትን ሁሉ አደርገዋለሁ፤

3) ፀሎትን ሳንደጋግም ከትምክህት ወጥተን በእምነት መፀለይ ያስፈልጋል፡ ፡

● ማቴ.6÷7

7. እናንተ ስትጸልዩ እንደ አሕዛብ ከንቱ ቃል አትድገሙ። እነርሱ ብዙ ቃላት በመናገራቸው እግዚአብሔር እንደሚሰማላቸው ያሰባሉ፡፡

4) በትህትና መንፈስ ስንፀልይ እግዚአብሔር ይደሰታል፡፡

● ሉቃ.18÷13

13. ቀራጩ ግን በሩቅ ቆሞ፣ ወደ ሰማይ ቀና ብሎ ለማየት እንኳ አልፈለገም፣ ነገር ግን በእጁ ደረቱን እየመታ፣ ‘እግዚብሔር ሆይ፣ እኔን ኀጢአተኛውን ማረኝ’ ይል ነበር፡፡

5) የእግዚአብሔርን ፈቃድ በመታዘዝ መፀለይ አለብን፡፡

● ሉቃ.4÷22

22. ሰዎችም ሁሉ ስለ ኢየሱስ በበጎ ይናገሩ ነበር፣ ደግሞም ከአፉም ከሚወጣው ከጸጋው ቃል እየተገረሙ፣ “ይህ የዮሴፍ ልጅ አይደለምን?” ይሉ ነበር፡፡

5. እግዚአብሔር የፀሎት መልስ በሶስት መንገድ ይመልሳል፡፡

1) የፀሎት መለስ ወዲያውኑ ይሰጣል፡፡

2) የሚንፀልየውን ፀሎት አስፈላጊ ካልሆነ መልስ አይሰጠንም፡፡ ይህ አይነት ፀሎት ላንተ አያስፈልግም በማለት ይዘጋል፡፡

እግዚአብሔርን ሊያስክድ ስለምችል እግዚአብሔር አስቀድሞ በማወቅ የማያስፈልገውን የፀሎት አይነት ሳይመልስ ይተዋል፡፡

3) የሚበልጠውን ሌሎች ነገሮችን በብዙ ጨምሮ ለመመለስ ታገሶ ይታገሳል፡፡ ይህ ማለት በምንፀልይበት ጊዜ ወቅቱን ያልጠበቀ ከሆነ፤ ነገር ግን ወደፊት ሊሰጥ ያለ ነገር ከሆነ፤ ጊዜው ሲደርስ ታግሶ ይሰጣል፡፡

6. ትክክለኛ የፀሎት አስተሳሰብ ምንድን ነው?

1) ስንፀልይ ምላሽ እንደሚመጣ በተስፋና በደስተኛ ልብ ወደ እግዚአብሔር መሄድ ያስፈልጋል፡፡ እግዚአብሔር ባሪያዎችን ስጠራ ስጦታን ለመስጠት ይጠራል፡፡

● መዝ.120÷1-7

1-በተጨነቅሁ ጊዜ ወደ እግዚአብሔር ጮኽሁ፥ ሰማኝም።

2-ከዓመፀኛ ከንፈር ከሽንጋይም አንደበት፥ አቤቱ፥ ነፍሴን አድናት።

3-ስለ ሽንገላ አንደበት ምን ይሰጡሃል? ምንስ ይጨምሩልሃል?

4-እንደ በረሃ እንጨት ፍም የኃያላን ፍላጾች የተሳሉ ናቸው።

5-መኖሪያዬ የራቀ እኔ ወዮልኝ በቄዳር ድንኳኖች አደርሁ።

6-ሰላምን ከሚጠሉ ጋር ነፍሴ ብዙ ጊዜ ኖረች።

7-እኔ ሰላማዊ ነኝ በተናገኋቸው ጊዜ ግን በከንቱ ተሰለፉብኝ።

2) የተስፋ ቃል ይዞ መፀለይ ያስፈልጋል፡፡

● ዘኁ.23÷19

19-ሐሰትን ይናገር ዘንድ እግዚአብሔር ሰው አይደለም፥ ይጸጸትም ዘንድ የሰው ልጅ አይደለም። እርሱ ያለውን አያደርገውምን? የተናገረውንስ አይፈጽመውምን?

3) ከፀሎት በኃላ ሳይጠራጠር የእምነትን ሰሐን በማዘጋጀት መጠበቅ ያስፈልጋል፡፡

● ያዕ.1÷6

6-ነገር ግን ሰው ምንም ሳይጠራጠር በእምነት ይለምን፤ የሚጠራጠር ሰው በነፋስ የተገፋና የተናወጠ የባሕር ማዕበል ይመስላል፡፡

4) አስቀድሞ እንደተቀበለ በማመንና በምስጋና ህይወት መጠበቅ

● ዮናስ.2÷2-7

2-ዮናስም በዓሣው ሆድ ውስጥ ሆኖ ወደ አምላኩ ወደ እግዚአብሔር ጸለየ፥እንዲህም አለ፦

3-በመከራዬ ሳለሁ ወደ አምላኬ ወደ እግዚአብሔር ጮኽሁ፥ እርሱም ሰማኝ በሲኦልም ሆድ ውስጥ ሆኜ ጮኽሁ፥ ቃሌንም አዳመጥህ።

4-ወደ ጥልቁ ወደ ባሕሩ ውስጥ ጣልኸኝ፥ ፈሳሾችም በዙሪያዬ ነበሩ ማዕበልህና ሞገድህ ሁሉ በላዬ አለፉ።

5-እኔም። ከዓይንህ ፊት ተጣልሁ ነገር ግን ወደ ቅዱስ መቅደስህ ደግሞ እመለከታለሁ አልሁ።

6-ውኆችም እስከ ነፍሴ ድረስ ከበቡኝ ጥልቁ ባሕር በዙሪያዬ ነበረ የባሕሩ ሣር በራሴ ተጠምጥሞ ነበር።

7-ወደ ተራሮች መሠረት ወረድሁ በምድርና በመወርወሪያዎችዋ ለዘላለም ተዘጋሁ አንተ ግን፥ አቤቱ አምላኬ፥ ሕይወቴን ከጕድጓዱ አወጣህ።

5) መልካም እግዚአብሔርን በተስፋ መጠበቅ

● ማቴ.7÷9-11

9. ከእናንተ መካከል ልጁ እንጀራ ቢለምነው፥ ለልጁ ድንጋይን የሚሰጠው ሰው ማን ነው?

10. ልጁ ዓሣን ቢለምነው ማን እባብን ይሰጠዋልን?

11. እንግዲህ እናንተ ክፉዎች ሳላችሁ፣ ለልጆቻችሁ መልካም ስጦታ መስጠትን ካወቃችሁ፥ ታዲያ፣ የሰማዩ አባታችሁማ ለሚለምኑት መልካም ስጠታን እንዴት አብልጦ አይሰጣቸውም?

★ ፀሎት፡- ክፍት ስብሰባ በዚህ አካባቢ እንዲያድግና ወደ ብዙ ቦታ እድሰራጭ ክርስቲያኖች ታማኝ የሆኑትን አገልጋዮች ክፍት ስብሰባ እንድሰብኩ መላክ እንድንችል ልንፀልይ ያስፈልጋል፡፡

ምዕራፍ 16

16. ያንተ እግዚአብሔር (ጌታ) ማን ነው? (ኢሳ.45÷5-7)

● ኢሳ.45÷5-7

5-6-እኔ እግዚአብሔር ነኝ ከእኔም ሌላ ማንም የለም ከእኔም በቀር አምላክ የለም በፀሐይ መውጫና በምዕራብ ያሉ ከእኔ በቀር ማንም ሌላ እንደሌለ ያውቁ ዘንድ አስታጠቅሁህ፥ አንተ ግን አላወቅኸኝም እኔ እግዚአብሔር ነኝ፥ ከእኔም ሌላ ማንም የለም።

7-ብርሃንን ሠራሁ፥ ጨለማውንም ፈጠርሁ ደኅንነትን እሠራለሁ፥ ክፋትንም እፈጥራለሁ እነነዚህን ሁሉ ያደረግሁ እግዚአብሔር እኔ ነኝ።

ሰዎች በአለም ላይ ብዙ መንገዶች እንደሚኖር ይናገራሉ፡፡ እንደዚህም ወደ እግዚአብሔር የሚወስደው መንገድ ብዙ ጎዳናዎች እንዳሉት ያወራሉ፡፡ አላህ እግዚአብሔር፤ ቢደክም ኢየሱስ አንድ አይነት እንደሆኑ ይናገራሉ፡፡ ነገር ግን ይህ የሰይጣን ሴራና ማታለል ነው፡፡ ሰይጣን ሰው እግዚአብሔርን እንዳያገኝ ስለሆነ ከቶ አይፈልግም፡፡ ሰይጣን እኛ ከእግዚአብሔር ጋር እንዳንገናኝና በጥሩ ደስታ እንዳንኖር ያደናቅፈናል፡፡ ሰይጣን አታላይ ስለሆነ እኛ የስህተት ሃይማኖት ይዘን ኃጢአትን እንድናርደግ፤ ጠንቋይን ተከትለን ወድቀን እንድንቀርና ፍፁም እንድንጠፋ ይፈልጋል፡፡

1. ሰዎች የስህተት አምልኮ እንዲያመልኩ ሰይጣን ያታልላል፡፡

1) ሰዎች ለክፉ መንፈስና ለሰይጣን ባሪያ ይሆናሉ፡፡

● ኤፌ.2÷2

2-በዚያን ጊዜ የዚህን ዓለም ክፋ አካሄድ ትከተሉ ነበር፤ እንዲሁም በአየር ላይ ያሉትን የመናፍስት ኀይሎች ለሚገዛው ትታዘዙ ነበር፤ እርሱ በማይታዘዙት ሰዎች ላይ የሚሠራ ርኩሱ መንፈስ ነው፡፡

2) የምኞት ባሪያ ይሆናሉ፡፡

● 1ዮሐ.2÷15-16

15-ዓለምን ወይም የዓለምን ነገር ሁሉ አትውደዱ፡፡ ዓለምን የሚወድ እግዚአብሔር አብን አይወድም፡፡

16-በዓለም ያለው ሁሉ የሥጋ ምኞት፣ የዐይን አምሮት፣ የኑሮ ትምክሕት ከዓለም ነው እንጂ ከእግዚአብሔር አብ አይደለም፡፡

3) ራሳቸውን በድርቀት ውስጥ ያስገባሉ፡፡

● 2ጢሞ.3÷2

2-ሰዎች ራሳቸውን የሚወዱ፣ ለገንዘብ የሚስገበገቡ፣ ትምክሕተኞች፣ ትዕቢተኞች፣ ተሳዳቢዎች፣ ለወላጆቻቸው የማይታዘዙ፣ ውለታቢሶች፣ ቅድና የሌላቸው፣

4) ክፉ መናፍስትንና ጣኦትን ያገለግላሉ፡፡

● ዘፀ.20÷4

4-በሰማይም ሆነ በምድር ወይም ከምድር በታች ባለው ውሃ ውስጥ ከሚኖሩት ነገሮች የማንኛውንም ዐይነት ምስል ጣዖት አድርገህ አትሥራ፤

5) በክፉ መናፍስት የተያዙ ይሆናሉ፡፡

● ኤፌሶን.6÷12

12-የእኛ ውጊያ ከሰዎች ጋር ሳይሆን በዚህ በጨለማ ዓለም ከሚሠሩ ገዢዎች፣ ከሥልጣናትና ከኀይላት እንዲሁም በሰማያዊ ስፍራ ካሉ ከርኩሳን መናፍስት ሰራዊት ጋር ነው፡፡

2. የስህተት አምልኮ የማገልገል ውጤት በመከራና በችግር ውስጥ መውደቅ ነው፡፡

1) እግዚአብሔር እንደሌለ ተናግሯል፡፡

● መዝ.53÷1

1-ሰነፍ በልቡ። አምላክ የለም ይላል። ረከሱ በበደላቸውም ጐሰቈሉ በጎ ነገርን የሚያደርጋት የለም።

2) የሃይማኖት ባሪያ መሆን፡፡

● ማቴ.12÷44-45

44. ርኩስ መንፈስ እንዲህ አለ፡፡ ‘እኔ ወደ ወጣሁበት ቤት ተመልሼ ልሂድ’ ይላል፣ ወደ ቤቱ ተመልሶ ሲመጣ፣ ቤቱ ባዶ ሆኖ፣ ጸድቶ፣ ተዘጋጅቶ ያገኘዋል፡፡

45. ከዚህ በኋላ፣ ርኩሱ መንፈስ ይሄድና ከእርሱ ይባስ የከፋትን ሌሎች ሰባት አጋንንት ይዞ ይመጣል፡፡ እነርሱም ሰውየው ውስጥ ገብተው ይኖራሉ፡፡ የዚያም ሰው የኋለኛው ሁኔታ ከፊተኛው ይልቅ የከፋ ይሆናል፡፡ በዚህ ክፉ ትውልድም ላይ እንዲሁ ይሆንበታል፡፡”

3) የኃጢያት ባሪያ መሆን፡፡

ግብረ ስጋ ግንኙነት የሚያደርጉ (አመንዛሪዎች) በክፉ መንፈስ ይሰራሉ፡፡ ለአንድ ሰው አንድ ሚስት ብቻ ሲያስፈልግ ከአንድ ሴት በላይ ተጨማሪ ሴቶችን ይገባሉ፡፡

● ሮሜ.6÷6

6. ከእንግዲህ የኀጢአት ባሮች እንዳንሆን፣ የኀጢአት ሰውነት እንዲወገድ አሮጌው ሰውነታችን ከክርስቶስ ጋር እንደ ተሰቀለ እናውቃለን፤

4) እርግማንና ፍርድን ይቀበላሉ፡፡

● ዕብ.9÷27

27-ለሰው አንድ ጊዜ መሞት ተመድቦለታል፤ ከሞት በኋላም ፍርድ አለበት፡፡

5) የዘላለም ስቃይና ፍርድ ይቀበላሉ፡፡

● ራዕ.11÷8

8-ሬሳቸውም በምሳሌያዊ አጠራር ሰዶም ወይም ግብጽ በምትባል በታላቂቱ ከተማ አደባባይ ይጋደማል፤ ይህች ከተማ የእነርሱ ጌታ የተሰቀለባት ናት፡፡

3. አሁን አንተ (አንቺ) ከዚህ ቦታ መውጣት ያስፈልጋል፡፡

1) አሁን አትዘገይ (ከሰይጣን ስቃይና ፍርድ ለመውጣት)

● 2ቆሮ.6÷1-2

1-ከእግዚአብሔር ጋር አብረን የምንሠራ እንደ መሆናችን የተቀበላችሁትን ጸጋ በከንቱ አታስቀሩት ብለን እንለምናችኋለን፡፡

2-እግዚአብሔር፣ “ተስማሚ በሆነ ጊዜ ሰማሁህ! በመዳን ቀን ረዳሁህ!” ስለሚል፣ “እነሆ ተስማሚ የሆነው ጊዜ አሁን ነው፤ የመዳኛው ቀን አሁን ነው፡፡”

2) ለወደፊት አትቅጠር ::

● ምሳሌ 27÷1

1-ቀን የሚያመጣውን ምን እንደ ሆነ አታውቅምና ነገ በሚሆነው አትመካ።

3) ያህዌ (እግዚአብሔር) እርሱ የእኛ እግዚአብሔር ነው፡፡ እርሱን ተቀበል፡፡

● ኢሳ.45÷5-6

5-6-እኔ እግዚአብሔር ነኝ ከእኔም ሌላ ማንም የለም ከእኔም በቀር አምላክ የለም በፀሐይ መውጫና በምዕራብ ያሉ ከእኔ በቀር ማንም ሌላ እንደሌለ ያውቁ ዘንድ አስታጠቅሁህ፥ አንተ ግን አላወቅኸኝም እኔ እግዚአብሔር ነኝ፥ ከእኔም ሌላ ማንም የለም።

4) ኢየሱስ ከእግዚአብሔር ጋር የሚያገናኝ መንገድ አዳኝም ነው፡፡

● ሐዋ.4÷12

12-መዳን ከኢየሱስ በቀር በሌላ በማንም የለም፤ እግዚብሔር ከሰማይ በታች እኛ ልንድንበት የሚገባን ሌላ ስም ለሰዎች የተሰጠ ስም የለም፡፡

● ሐዋ.16÷31፣

31-ጳውሎስና ሲላስም፣ “በጌተ በኢየሱስ እመን፤ አንተም ቤተ ሰዎችህም ትድናላችሁ” አሉት፡፡

● ዮሐ.14÷6

6. ኢየሱስም እንዲህ ሲል መለሰለት፣ “እኔ መንገድና እውነት ሕይወትም ነኝ፤ በእኔ በኩል ካልሆነ በቀር ማንም ወደ አብ የሚመጣ የለም፡፡

4. ከእግዚአብሔር ጋር ተስማምቶ መኖር በጣም አስፈላጊ ነው፡፡

1) እግዚአብሔርን አስቀድመን ማግኘት ያስፈልጋል፡፡

● ዮሐ.17÷3

3. አንተን ብቻ እውነተኛውን አምላክና የላክኸውንም ኢየሱስ ክርስቶስን ማወቅ ነው፡፡

2) ኢየሱስ ክርስቶስን አዳኝና ጌታ አድርገን መቀበል ያስፈልጋል፡፡

● ዮሐ.1÷12

12. ነገር ግን ኢየሱስ ራሱ ለተቀበሉትና በስሙ ላመኑት ሰዎች ሁሉ የእግዚአብሔር ልጆች የመሆንን መብት ሰጣቸው፡፡

3) ኢየሱስን ስናምን ኢየሱስ ለቀድሞ ችግራችን፤ ለአሁኑ ችግሮችና ለወደፊቱ ችግሮች ወዲያውኑ መፍትሄ ይሰጣል፡፡

● ኤፌ.2÷5-6

5-በበደላችን የሞትን ብንሆንም እንኳ እግዚአብሔር ከክርስቶስ ጋር እንድንኖር አድርጎናል፤ እናንተም የዳናችሁት በጸጋው ነው፡፡

6-እግዚአብሔር በክርስቶስ ኢየሱስ አማካይነት ከእርሱ ጋር ከሞት አስነሥቶ በሰማያዊው ስፍራ ከእርሱ ጋር አስቀመጠን፡፡

4) ለተከታታይ የሚሆን በረከት በመቀበል ይኖራል፡፡

● ኤፌ.2÷7

7-ይህንንም ያደረገው በኢየሱስ ክርስቶስ ለእኛ የገለጠውን ቸርነትና ወደር የሌለውን የጸጋውን ብልጽግና በሚመጡት ዘመናት ሊያሳየን ብሎ ነው፡፡

5) አሁን እኛ በህይወት ብቻችን አይደለንም ምክንያቱም ኢየሱስ ክርስቶስ ከእኛ ጋር አለ፡፡

● ገላ.2÷20

20-እኔ ከክርስቶስ ጋር እንደ ተሰቀልኩ ያህል ስለምቈጥር ከእንግዲህ ወዲህ ክርስቶስ በእኔ ውስጥ ይኖራል እንጂ እኔ ለራሴ ሕይወት የምኖር አይደለሁም፤ አሁንም በሥጋዊ አካሌ የምኖረው በወደደኝና ስለ እኔ ራሱን አሳልፎ በሰጠው በእግዚአብሔር ልጅ በማመን በተገኘው ሕይወት ነው፡፡

5. ኢየሱስን የሚያምኑ ሰዎች በበረከት ውስጥ ይኖራሉ፡፡

1) የእግዚአብሔር ልጅ የመሆን በረከት ውስጥ ይኖራሉ፡፡

● ዮሐ.1÷12

12. ነገር ግን ኢየሱስ ራሱ ለተቀበሉትና በስሙ ላመኑት ሰዎች ሁሉ የእግዚአብሔር ልጆች የመሆን መብት ሰጣቸው፡፡

2) ከመንፈስ ቅዱስ ጋር የመኖር በረከት፡፡ ይህ ማለት በመንፈስ ቅዱስ ቁጥጥር ስር የመሆን በረከት ማለት ነው፡፡

● ዮሐ.14÷16-17

16. እኔ አብን እለምናለሁ፣ እርሱም ከእናንተ ጋር ለዘላለም የሚኖር ሌላ አጽናኝ ይሰጣችኋል፣

17. እርሱም የእውነት መንፈስ ነው፣ ዓለም እርሱን ስለማያየውና ስለማያውቀው ሊቀበለው አይችልም፡፡ እናንተ ግን፣ እርሱ ከእናንተ ጋር ስለሚኖርና በውስጣችሁም ስላለ ታውቁታላችሁ፡፡

3) የፀሎት መላሽ የማግኘት በረከት ውስጥ ይኖራሉ::

● ዮሐ.16÷24

24. እስከ አሁን እናንተ በስሜ ምንም ነገር አለመናችሁም፣ ለምኑ ይሰጣችኋል፣ ደስታችሁም ፍጹም ይሆናል፡፡

4) በኢየሱስ ስም የሰይጣንን ስልጣን በማሸነፍ በበረከት ውስጥ ይኖራሉ፡፡

● ማቴ.16÷18

18. እኔም እንዲህ እልሃለሁ፣ አንተ (ጴጥሮስ)፣ አለት ነህ፣ በዚህችም የመሠረት ድንጋይ ላይ ቤተ ክርስቲያኔን እሠራለሁ፣ ይህችንም ቤተ ክርስቲያን የሞት ኀይል እንኳ አያሸንፋትም፡፡

5) የመላዕክት ርዳታ በማግኘት በረከት ውስጥ ይኖራሉ

● ዕብ.1÷14

14-ታዲያ፣ መላእክት ሁሉ የሚድኑትን ሰዎች ለማገልገል የሚላኩ የእግዚአብሔር አገልጋዮች የሆኑ መናፍስት አይደሉምን?

6) የመንግስተ ሰማይ ዜጎች (ወራሾች) የመሆን በረከት ውስጥ ይኖራሉ

● ፊልጵ.3÷20

20-እኛ ግን የሰማይ መንግሥት ዜጎች ነን፤ ከዚያም የሚመጣውን አዳኝ ጌታችንን ኢየሱስ ክርስቶስን በናፍቆት እንጠባበቃለን፡፡

7) የዓለም ሀብት የመቀበል በረከት ውስጥ ይኖራሉ፡፡

● ማቴ.28÷18-20

18-ኢየሱስ ወደ ደቀ መዛሙርቱ ቀረበና እንዲህ አላቸው፣ "ሥልጣን ሁሉ በሰማይና በምድር ተሰጥቶኛል፣

19-ስለዚህ እናንተ ወደ ዓለም ሕዝብ ሁሉ ሂዱ፣ በአብ፣ በወልድና በመንፈስ ቅዱስ ስም እያጠመቃችኋቸው የእኔ ደቀ መዛሙርት አድርጉአቸው፡፡

20-እኔ ለእናንተ ያዘዝኋችሁን ሁሉ እንዲጠብቁ አስተምሯቸው፣ እነሆ፣ እኔም እስከ ዓለም መጨረሻ ድረስ ሁልጊዜ ከእናንተ ጋር ነኝ፡፡"

8) የእግዚአብሔር መንግሥት ተወካዮች የመሆን በረከት ውስጥ ይኖራሉ፡፡

● ዘፍ.1÷28

28-እግዚአብሔርም "ብዙ፣ ተባዙ፣ ዘራችሁ ምድርን ይሙላ፤ ምድርም በቍጥጥራችሁ ሥር ትሁን፤ በባሕር ውስጥ በሚኖሩ ዓሣዎች፣ በሰማይ በሚበርሩ ወፎችና በምድር ላይ በሚንቀሳቀሱ ሕያዋን ፍጥረቶች ሁሉ ላይ ሥልጣን ይኑራችሁ" ብሎ ባረካቸው፡፡

9) የእግዚአብሔር ቤተ መቅደስ የመሆን በረከት ውስጥ ይኖራሉ፡፡

በአለት ላይ የተመሰረተ ቤተ-ክርስቲያን የሲኦል ስልጣን ማሸነፍ አይችልም፤ የመንግስተ ሰማይ መክፈቻ ቁልፍ የተሰጠ ሰው ነው፡፡

● ማቴ.16÷18-20

18. እኔም እንዲህ እልሃለሁ፣ አንተ (ጴጥሮስ)፣ አለት ነህ፣ በዚህችም የመሠረት ድንጋይ ላይ ቤተ ክርስቲያኔን እሠራለሁ፣ ይህችንም ቤተ ክርስቲያን የሞት ኀይል እንኳ አያሸንፋትም፡፡

19. የመንግሥተ ሰማይን መክፈቻዎች እሰጥሃለሁ፣ በምድር ያሰርኸው ሁሉ በሰማይ የታሰረ ይሆናል፣

በምድርም የፈታኸው ሁሉ በሰማይ የተፈታ ይሆናል፡፡”

20. ከዚህ በኋላ ኢየሱስ ደቀ መዛሙርቱን እርሱ ክርስቶስ መሆኑን ለማንም እንዳይናገሩ አዘዛቸው፡፡

10) የአብርሃምን በረከቶች በመቀበል በረከት ውስጥ ይኖራሉ

① በእያንዳንዱ ሰው መባረክ

② በቤተሰብ መባረክ

③ በዘመዶች መባረክ

④ በአገር መባረክ

⑤ በሁሉም አገሮች (በአለም) መባረክ

● ገላ.3÷14

14-ይህም የሆነው እግዚአብሔር ለአብርሃም የሰጠው በረከት በኢየሱስ ክርስቶስ አማካይነት ለአሕዛብ እንዲደርስና እኛም እግዚአብሔር እሰጣችኋለሁ ያለውን መንፈስ ቅዱስን በእምነት እንድንቀበል ነው፡፡

ምዕራፍ 17

17. የመከናወን ሕይወት ዘዴ (ሮሜ.1÷16-17)

● ሮሜ.1÷16-17

16. እኔ በወንጌል ቃል አላፍርም፤ ምክንያቱም ለሚያምን ሁሉ ለድነት የማሆን የእግዚአብሔር ኀይል ነው፤ ይህም በመጀመሪያ ለአይሁድ፣ ቀጥሎም ለአሕዛብ ነው፡፡

17. በወንጌል የእግዚአብሔር ጽድቅ ተገልጦአልና፤ ጽድቁም ከመጀመሪያ እስከ መጨረሻ በእምነት የሆነ ነው፣ "ጻድቅ በእመነት ይኖራል" ተብሎ እንደ ተጻፈው፡፡

የመከናወን ሕይወት ምን ዓይነት ቅርፅ አለው?

ሰዎች ሁሉ የመከናወን ሕይወት ለመኖር ወደ ግብ ለመድረስ ይሮጣሉ፡፡ ነገር ግን እያንዳንዱ ሰው የራሱን ግብ በቀላሉ ለመውሰድ አይችልም፡፡ የመከናወንን ሕይወት ፈልጎ ግን ብዙ ሰዎች የጥፋት ልምምድ ያደርጋሉ፡፡ ለምን ይህንን ሥራ ያደርጋሉ? ምክንያቱም ኢየሱስ የሌለበት ጉዞ ስለሆነ ነው፡፡

ለሕይወት መፍትሄ የሚሰጥ ወንጌልን (ኢየሱስን) ስለላወቀ ውድቀትን ያመጣል፡፡

1. ሰይጣን ኢየሱስን እንዳናውቅ ይፈትነናል፡፡

1) ሰይጣን ውሸታምና አታላይ ስለሆነ ነፍስ እንድትሞት ይፈልጋል፡፡

● ዮሐ.8÷44

44. እናንተ የአባታችሁ የዲያብሎስ ልጆች ናችሁ፣ የአባታችሁንም ፍላጎት ለመፈጸም ትሻላችሁ፡፡ እርሱ ከመጀመሪያ ነፍሰ ገዳይ ነበር፣ በዲያብሎስ እውነት ስለሌለ በእውነት አልቆመም፣ ዲያብሎስ ሐሰተኛና የሐሰት አባት ስለ ሆነ ሐሰት በሚናገርበት ጊዜ ከገዛ ራሱ አውጥቶ ይናገራል፡፡

2) ሰይጣን ራሱን የፅድቅ ብርሃን መልአክ ለመምሰል ራሱን ይለዋወጣል፡፡

● 2ቆሮ.11÷14

14-ይህም የሚያስደንቅ ነገር አይደለም፤ ሰይጣን እንኳ የብርሃን መልአክ ለመምሰል ራሱን ይለውጣል፡፡

3) ብዙ ንብረት በማስመኘት ይፈትነናል፡፡ በሥጋ ምኞት በዓይን አምሮት በኑሮ ትምክት እኛን ይፈትናል፡፡

● 1ዮሐ.2÷15-16

15-ዓለምን ወይም የዓለምን ነገር ሁሉ አትውደዱ፡፡ ዓለምን የሚወድ እግዚአብሔር አብን አይወድም፡፡

16-በዓለም ያለው ሁሉ የሥጋ ምኞት፣ የዐይን አምሮት፣ የኑሮ ትምክሕት ከዓለም ነው እንጂ ከእግዚአብሔር አብ አይደለም፡፡

4) በጨለማ ዓለም ውስጥ እንድንገባ ይፈትነናል፡፡

● ኤፌ.6÷12

12-የእኛ ውጊያ ከሰዎች ጋር ሳይሆን በዚህ በጨለማ ዓለም ከሚሠሩ ገዢዎች፣ ከሥልጣናትና ከኀይላት እንዲሁም በሰማያዊ ስፍራ ካሉ ከርኩሳን መናፍስት ሰራዊት ጋር ነው፡፡

2. ጌታ ኢየሱስ የሰይጣንን ሥልጣን በመስቀል ላይ አሸንፎ ሥራውንም ሁሉ አፍርሶ፡-

1) እኛን አዳነን፡፡

● ቆላ.2÷13

13-ኃጢአት በመሥራታችሁና የኃጢአተኛው ሥጋችሁ በክርስቶስ በማመን ባለመገረዙ ምክንያት ሙታን ነበራችሁ፤ አሁን ግን እግዚአብሔር ከክርስቶስ ጋር ሕያዋን አድርጓችኋል፤ ኃጢአታችሁንም ሁሉ ይቅር ብሎላችኋል፡፡

2) የእኛን እርግማን ለራሱ ወስዶ፤ በመስቀል ላይም ተሰቅሎ ከርግማን ነፃ አወጣን፡፡

● ቆላ.2÷14

14-እርሱ ያንን ይከሰንና ይቃወመን የነበረውን በሕግ ያለውን የዕዳ ጽሑፍ ደመሰሰው፤ በመስቀል ላይ ቸንክሮም ከእኛ አስወገደው፡፡

3) የጨለማ ሥልጣናትን አስወግዶ እኛን ነፃ አወጣን፡፡

● ቆላ.2÷15

15-ኀይላችንና ባለሥልጣናትን በመስቀሉ ድል ነሥቶ ትጥቃቸውን ካስፈታ በኋላ ምርኮኞች ሆነው በይፋ እንዲታዩ አደረጋቸው፡፡

4) በመስቀል ላይ ተሰቅሎ ሁሉንም አሸነፈ፡፡

● ቆላ.2÷15

15-ኀይሎችንና ባለሥልጣኖችን በመስቀሉ ድል ነሥቶ ትጥቃቸውን ካስፈታ በኋላ ምርኮኞች ሆነው በይፋ እንዲታዩ አደረጋቸው፡፡

3. ኢየሱስ የመስቀል ሞት ማሸነፉ ለእኛ ታላቅ ደስታና የምስራች ነው፡፡ ይህ ማለት ወንጌል ማለት ነው፡፡

1) ኢየሱስ ለሕይወታችን ችግሮች መፍትሄ የሚሰጥ ነው፡፡

● ገላ.3÷13

13-"በእንጨት ላይ ተሰቅሎ የሚሞት ሁሉ የተረገመ ነው" ተብሎ ስለ ተጻፈ ክርስቶስ ስለ እኛ እንደ ተረገመ ሰው ሆኖ ሕግ ከሚያስከትለው ርግማን ዋጀን፡፡

2) ኢየሱስ ከእግዚአብሔር ዘንድ ለእኛ ፍፁም በረከትን አመጣ፡፡

● ገላ.3÷14

14-ይህም የሆነው እግዚአብሔር ለአብርሃም የሰጠው በረከት በኢየሱስ ክርስቶስ አማካይነት ለአሕዛብ እንዲደርስና እኛም እግዚአብሔር እሰጣችኋለሁ ያለውን መንፈስ ቅዱስን በእምነት እንድንቀበል ነው፡፡

3) ኢየሱስ ወንጌልን እንድናከናውን ሕይወትን ሰጠ፡፡

● ሮሜ.1÷16

16. እኔ በወንጌል ቃል አላፍርም፤ ምክንያቱም ለሚያምን ሁሉ ለድነት የሚሆን የእግዚአብሔር ኀይል ነው፤ ይህም በመጀመሪያ ለአይሁድ፣ ቀጥሎም ለአሕዛብ ነው፡፡

4) በዚህ ቃል ተስማምተን በእርሱ መኖር ያስፈልጋል፡፡

● ሮሜ.10÷8-10

8. ነገር ግን ምን ይላል? "ቃሉ በአጠገብህ ነው፤ በአፍህና በልብህም ውስጥ ነው፤" የምንሰብከውም የእምነት ቃል ይህ ነው፤

9. ኢየሱስ ጌታ መሆኑን በአፍህ ብትመሰክርና እግዚአብሔር ከሞት እንዳስነሣውም በልብህ ብታምን ትድናለህ፡፡

10. ሰው በልቡ ሲያምን ይጸድቃል፤ በአፉም ሲመሰክር ይድናል፤

4. ነገር ግን ሰይጣን ወንጌልን እንዳንመለከት ያደርጋል፡፡

1) ሰይጣን ወንጌል ነፍስ ብቻ የሚያድን ነው ብሎ ይናገራል፡፡

2) ሰይጣን ወንጌል መልካም ሥራ ብቻ እንዲንሠራ ያደርጋል በማለት ያሳስታል፡፡

3) ሰይጣን ወንጌል ዕውቀት ብቻ ይሰጣል በማለት ሰዎችን ያሳስታል፡፡

4) ሰይጣን ወንጌል የማህበራዊ ተሃድሶ ብቻ ያመጣል በማለት ያሳስታል፡፡

5) ሰይጣን ወንጌል እንደጠንቋይ ነው በማለት ያሳስታል፡፡

6) የእውነት ወንጌልን ባለማወቅ በሕይወት ላይ ጥፋትን ያመጣል፡፡

5. የመከናወን ሕይወት ዘዴ

1) እግዚአብሔርን መቀበል ያስፈልጋል፡፡

● ዮሐ.1÷12

12. ነገር ግን ኢየሱስ ራሱ ለተቀበሉትና በስሙ ላመኑት ሰዎች ሁሉ የእግዚአብሔር ልጆች የመሆን መብት ሰጣቸው፡፡

2) ወንጌልን በትክክለኛው መንገድ ማወቅ ያስፈልጋል፡፡

● ሮሜ.1÷16-17

16. እኔ በወንጌል ቃል አላፍርም፤ ምክንያቱም ለሚያምን ሁሉ ለድነት የሚሆን የእግዚአብሔር ኀይል ነው፤ ይህም በመጀመሪያ ለአይሁድ፣ ቀጥሎም ለአሕዛብ ነው፡፡

17. በወንጌል የእግዚአብሔር ጽድቅ ተገልጦአልና፤ ጽድቁም ከመጀመሪያ እስከ መጨረሻ በእምነት የሆነ ነው፣ "ጻድቅ በእመነት በህይወት ይኖራል" ተብሎ እንደ

ተጻፈው፡፡

3) በወንጌል መኖር ያስፈልጋል፡፡

● ገላ.3÷13-14

13-"በእንጨት ላይ ተሰቅሎ የሚሞት ሁሉ የተረገመ ነው" ተብሎ ስለ ተጻፈ ክርስቶስ ስለ እኛ እንደ ተረገመ ሰው ሆኖ ሕግ ከሚያስከትለው ርግማን ዋጀን፡፡

14-ይህም የሆነው እግዚአብሔር ለአብርሃም የሰጠው በረከትን በኢየሱስ ክርስቶስ አማካይነት ለአሕዛብ እንዲደርስና እኛም እግዚአብሔር እሰጣችኋለሁ ያለውን መንፈስ ቅዱስን በእምነት እንድንቀበል ነው፡፡

4) በወንጌል ይህንን ዓለም ማሸነፍ ያስፈልጋል፡፡

● ማር.16÷15-20

15. እንዲህም አላቸው፣ "ወደ መላው ዓለም ሂዱ፣ ለሰው ሁሉ ወንጌልን ስበኩ፣

16. ያመነና የተጠመቀ ይድናል፣ የማያምን ግን ይፈረድበታል፡፡

17. የሚያምኑት እነዚህን ምልክቶች ያደርጋሉ፣ በስሜ አጋንንትን ያወጣሉ፣ በአዲስ ቋንቋም ይናገራሉ፣

18. እባቦችን ቢይዙ፣ ወይም የሚገድል መርዝ እንኳ ቢጠጡ አይጐዳቸውም፣ እጃቸውን በበሽተኞች ላይ ሲጭኑ በሽተኞቹ ይድናሉ፡፡"

19. ጌታ ኢየሱስ ይህን ሁሉ ከነገራቸው በኋላ ወደ ሰማይ ዐረገ፡፡ በእግዚአብሔርም ቀኝ ተቀመጠ፡፡

20. ደቀ መዛሙርቱም በየስፍራው ሁሉ እየሄዱ ሰበኩ፣ ጌታም ከእነርሱ ጋር ይሠራ ነበር፣ ትምህርታቸውንም ተከትለው በሚፈጸሙ ምልክቶች ቃሉን ያጸና ነበር፡፡